Geography in Amharic.

From the Chh. Miss^y Soc^y.

Presented at Comm^ee Meet^g

Aug^t 1. 1842.

# ጌዎግራፊያ ፡

# የምድር ፡ ትምህርት ።

# ጌዎግራፊያ ፡

ማለቱ ፡

## የምድር ፡ ትምህርት ።

ላበሻ ፡ ተማሮች ፡ ለረባቸው ፡ ተጻፈች ፡

በእንግሊዝም ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በሚስዮን ፡ ጉባኤዋ ፡ ፈቃድ ፡

ታተመች ፡



በሎንደን ፡ በእንግጣር ፡ ከተማ ፡ ከዚያም ፡ በሪቸርድ ፡
ወትስ ፡ ማኅተምያ ፡ በልደት ፡ አመት ፡ ፲፰፻፵፩ ።

# መቅድም ፡፡

በአብና ፡ በወልድ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ስም ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡፡ አሜን ፡፡

ወደጄ ፡ ተማሪና ፡ አንባቢ ፡ ሆይ ፡፡ ይህችን ፡ መጽሐፍ ፡ እነሆ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ረድኤት ፡ ጻፍሁልህ ፡ የምድርን ፡ ትምርት ፡ ተምረህ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ጥበብና ፡ ፍቅር ፡ ታይ ፡ ዘንድ ፡ እንዲህ ፡ ያለውን ፡ መኖርያ ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ፈጥርዋልና ፡ አሕዛብንም ፡ ሁሉን ፡ በየምድራቸው ፡ አስቀምጥዋልና ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሁነው ፡ የሚመጣውን ፡ ዓለምን ፡ ደህንነት ፡ ይሹ ፡ ዘንድ ፡ በክርስቶስ ፡ ሃይማኖት ፡፡ ይህችን ፡ መጽሐፍ ፡ በጣም ፡ ብትማር ፡ በቤት ፡ ተቀምጠህ ፡ ወደ ፡ ሩቅ ፡ አገር ፡ እንደሚሔድ ፡ ሰው ፡ ትሆናለህ ፡ በቀደምም ፡ ስማቸውን ፡ እንኳ ፡ ያልሰማሀውን ፡ አሕዛብ ፡ መኖርያቸውን ፡ ጠባያቸውንም ፡ ስራቸውንም ፡ ንብረታቸውንም ፡ ከዚህ ፡ ታገኛለህ ፡፡ ሁላቸውም ፡ ወንድሞችህ ፡ ናቸው ፡ ሁላቸውም ፡ ታላቆችና ፡ ታናሾች ፡ ብልሃተኞችና ፡ አራዊትም ፡ በጎችና ፡ ክፎችም ፡ ዘመዶችህ ፡ ያባትህ ፡ የአደም ፡ ልጆች ፡፡ እወቃቸው ፡ ተማርባቸውም ፡ ስራቸውንም ፡ መርመር ፡ የምታገኝባቸውንም ፡ በጎ ፡ ነገርን ፡ ጠብቅ ፡ ከክፉም ፡ ሽሽ ፡፡ ሁላቸውንም ፡ ውደድ ፡ ነፍስህን ፡ ትወድ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደሚሻ ፡፡ ከ

## መቅደም ፡፡

ሁሉም ፡ ይልቅ ፡ ነፍስህን ፡ ጥየቅ ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡፡ እግ ዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ምንድር ፡ ፈጠረኝ ፡፡ የእግዚአብሔርም ፡ ፈ ቃድ ፡ በኔ ፡ ምንድር ፡ ነው ፡፡ እኔም ፡ እንዴት ፡ እፈጽማለ ሁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡፡ ምንድርም ፡ ነው ፡ የእግ ዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ በሕዝቢ ፡ በወገኖቼም ፡፡ እኛም ፡ የሐ በሻ ፡ ሰዎች ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚሻብን ፡ እናድርገዋለን ን ፡፡ ባላደረግነውም ፡ ምን ፡ ይገባናል ፡ እንጊዲህ ፡ እናድር ግ ፡ ዘንድ ፡፡ እንዲሁም ፡ ብትጠይቅ ፡ መጽሐፈ ፡ ቅዱስ ፡ በጣም ፡ ይመልስልሃል ፡ እርሱንም ፡ ስማ ፡ ተከተለውም ፡፡ አሜን ፡፡

የእግዚአብሔርንም ፡ በረከት ፡ ይለምንልሃል ፡ ወደጅህ ፡

ቻርልስ ፡ ዊልየም ፡ ኢዘንበርግ ፡
የወንጌል ፡ መለክተኛ ፡፡

## መክፈቻ ፡

ላያሌ ፡ በዚች ፡ መጽሐፍ ፡ ላሉ ፡ ምልክቶች ፡ ለታጸሩም ፡ በሀበሻም ፡ ላልታወቁ ፡ ቃላት ፡፡

° አርዝ ፡ ማለቱ ፡ ማዕረግ ፡፡ ዙርያ ፡ ሁሉ ፡ በ፫፻፷፡ በተካከሉ ፡ ክፍሎች ፡ ይከፈላል ፡ ክፍልም ፡ ሁሉ ፡ አርዝ ፡ ወይስ ፡ ማዕረግ ፡ ይባላል ፡፡ የምድር ፡ አርዞች ፡ መኻከለኛ ፡ ርዝመት ፡ ፷፱፡ ሚላ ፡ ወይስ ፡ ለግረኛ ፡ የሶስት ፡ ቀን ፡ ተኩል ፡ መንገድ ፡ ነው ፡፡ ፬°፡ ማለት ፡ አራት ፡ አርዝ ፡ ነው ፡፡

′ ደቂቅ ፡ የሰዓት ፡ ክፍል ፡ ከ፷፡ አንድ ፡፡ በጌዎግራፊያም ፡ አርዝ ፡ ደግሞ ፡ በ፷፡ ክፍል ፡ ይከፈላል ፡ ክፍልም ፡ ሁሉ ፡ ደቂቅ ፡ ይባላል ፡፡ ፲′፡ ማለቱ ፡ አሥር ፡ ደቂቅ ፡ ማለት ፡ ነው ፡፡

—፡ እስከ ፡ ድረስ ፡ ማለት ፡ ነው ፡፡ ፴°፡ — ፵°፡ ማለት ፡ ከሠላሳ ፡ አርዝ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አርባ ፡ አርዝ ፡ ድረስ ፡ ነው ፡፡

ስ ፡ ማለቱ ፡ ስፍራ ፡ በአርዝና ፡ በደቂቅ ፡ ተሰፍሮ ፡ እንደ ፡ ታወቀ ፡፡

ወ ፡ ወሰን ፡፡

ታት ፡ ታላቅነት ፡፡ ታ ፡ ታላቅ ፡ ወይስ ፡ ታላቆች ፡፡

ወድ ፡ ወርድ ፡ የስፍራ ፡ ርቀት ፡ ካስተካካይ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ወይስ ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡፡

ርት ፡ ርዝመት ፡ የስፍራ ፡ ርቀት ፡ በግሪኒች ፡ ከሚያልፍ ፡ ከመጀመርያ ፡ ሥረደያን ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ወይስ ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡፡

ምቅ ፡ ምሥራቅ ፡፡ ሰ ፡ ሰሜን ፡፡

ምብ ፡ ምዕራብ ፡፡ ደ ፡ ደቡብ ፡፡

ሚ ላ ፡ የርቀት ፡ መስፈርያ ፡፡ አንድ ፡ አርዝ ፡ ፷፱፡ ሚላ ፡ እንግሊዝ ፡ አለው ፡ ወይስ ፡ ፲፭፡ ሚላ ፡ ንምሳዊ ፡፡ በዚች ፡ መጽሐፍ ፡ ሚላ ፡ ሲል ፡ ሚላ ፡ እንግሊዝ ፡ ነው ፡ እርሱም ፡ ፱፷፪፡ እርምጃ ፡ አለው ፡፡

ሚ ልዮ ን ፡ ቍጥር ፡ ነው ፡ መቶ ፡ እልፍ ፡፡

# መክፈቻ ፡፡

ቢብልዮቴካ ፡ ማለት ፡ የመጻሕፍት ፡ መሰብሰቢያ ፡ ነው ፡፡

ኡኒዌርሲታስ ፡ ታላቅ ፡ ማስተማርያ ፡ ነው ፡ ለቀሳወስት ፡ ለሕጋውያንም ፡ ለባለ ፡ መድኃኒቶችም ፡ ለፈሎሶፎችም ፡፡

ኮለጅና ፡ አክደሚያ ፡ ግምናስዩምም ፡ የታላቆች ፡ ማስተማርዮች ፡ አይነት ፡ ናቸው ፡ ከኡኒዌርሲታስ ፡ ግን ፡ ያንሳሉ ፡፡

ሚትሮጶሊታን ፡ ማለት ፡ መጀመርያ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ነው ፡ አንደ ፡ መጥራን ፡፡ በግእዝም ፡ መጥረብሊጥ ፡ ማለቱ ፡ ጳጳስ ፡ ይባላል ፡፡

ሚስዮን ፡ ማለት ፡ መልእክት ፡ ነው ፡፡ የሚስዮን ፡ ጉባኤ ፡ ማለት ፡ የምድርን ፡ አሕዛብ ፡ በወንጌል ፡ ለማስተማር ፡ የክርስቶስንም ፡ እውቀት ፡ በመኻከላቸው ፡ ለመዘረጋት ፡ ቀሳወስትንና ፡ መምህራንን ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ የሚልኩ ፡ የተገናኙ ፡ በፈቃደቸውም ፡ ለጉባኤ ፡ ክርስቲያን ፡፡

የቀረ ፡ መሥጢር ፡ ሁሉ ፡ መምህር ፡ ሊፈታ ፡ ነው ፡፡

## ጌዎግራፊያ፡

## የምድር፡ ትምህርት።

ጌዎግራፊያ፡ በ፫፤ ክፍል፡ ትከፈላለች።

፩፤ ክፍል። ጌዎግራፊያ፡ መትማቲቄ።
፪፤ . . . . . . . . . . . ፊሲቄ።
፫፤ . . . . . . . . . . . ፖሊቲቄ።

## መጀመርያ፡ ክፍል።

### ጌዎግራፊያ፡ መትማቲቄ።

ጌዎግራፊያ፡ መትማቲቄ፡ ታስተምረናለች፡ ምድራችን፡ እንዴት፡ እንደ፡ ገጠመች፡ ከሌላ፡ ካለም፡ ፍጥረት፡ ከፀሓይና፡ ከጨረቃ፡ ከከዋክብትም፡ ጋራ። የምድርንም፡ ታላቅነት፡ ታስታውቀናለች።

ያለምም፡ ፍጥረት፡ እጅግ፡ ነው፡ ቍጥርንም፡ አጣ። እግዚአብሔር፡ ብቻ፡ እርሱ፡ ኃይሉን፡ ጥበቡንም፡ ታላቅነቱንም፡ ፍቅሩንም፡ ለመግለጽ፡ የፈጠራቸው፡ ሁላቸውን፡ ያውቃል፡ በየስማቸውም፡ ይጸራቸዋል። ይሳይያስ፡ ፵፤ ፳፮። እኛ፡ የምናውቀው፡ ከከዋክብት፡ ነገር፡ ጥቂት፡ ነው። አዋቆችም፡ እንኳ፡ ዕለት፡ ዕለት፡ ይማረበታል። በሚማሩም፡ መጠን፡ እጅግ፡ በቀደም፡ ያልታወቀውን፡ ነገር፡ ያገኛሉ።

ከዋክብትንም፡ ሁሉን፡ በ፫፤ ወገን፡ እንከፍላለን። እርሳቸውም፡

፩፤ የሚጸኑ፡ ከዋክብት፡ ስፍራቸውን፡ የማይለውጡ፡ ብርሃናቸውም፡ በየራሳቸው፡ ያላቸው።

፪፤ ጵላኔቶች፡ ማለት፡ በየሥርዓታቸው፡ የሚዞሩ፡ ስፍራቸውንም፡ ወትሩ፡ የሚለውጡ፡ በየራሳቸውም፡ ተጨለመው፡ ብርሃናቸውን፡ ከፀሓይ፡ የሚቀበሉ፡ ከዋክብት።

፫፤ ኮሜቶች፡ ጅራት፡ ያላቸው፡ ከዋክብት።

## ስለ : ፀሓይ : ፀሓይንም : ከበውት : ስለሚዞሩ : ከዋክብት ::

ፀሓይ : ብርሃን : ለብሶ : የሚዞሩትን : ከዋክብት : ያበራል :: እርሱም : እንደ : ከዋክብት : ሁሉ : አረርን : ይመስላል : ከምድርና : ፀሓይን : ከሚዞሩ : ከዋክብትም : ሁሉ : ይበልጣል :: ስፍራውንም : አይለውጥም : በሀያ : አምስት : ቀን : ተኩል : ግን : አንድ : ጊዜ : በራሱ : ይዞራል ::

የፀሓይም : ጵላኔቶች : ፀሓይን : የሚዞሩ : ከዋክብት : ፲፩፤ ናቸው :: ፀሓይንም : ሲዞሩ : መንገዳቸው : እንቍላልን : ይመስላል :: እርሳቸውም : አንድ : ጊዜ : ለፀሓይ : ይቀርባሉ : አንደግዜም : ከርሱ : ይርቃሉ :: ይህም : ጵሪሄልዮን : አፌልዮንም : መኻከለኛ : ርቀታቸውም : ይባላል :: ስማቸውና : ሥርዓታቸውም : ይህ : ነው ::

፩፤፤ መጀመርያ : ጵለኔታ : ለፀሓይም : ከሁሉ : ይልቅ : የሚቀርብ : መርኩርዮስ : ነው :: ምልክቱም : ይህ : ነው :: ☿ :: መኻከለኛ : መስፈርያውም : ፫፪፵፰፤ ሚላ : ነው : ከምድር : መኻከለኛ : መስፈርያም : ፪፤ ዕጽፍ : ተኩል : ያንሳል :: ርቀቱም : ከፀሓይ : ፶፯፤ ሚልዮን : ፳፵፩ ሺህም : ፱፳፳፤ ሚላ : ነው :: ሩጫውንም : ፀሓይን : ዙሮ : በ፹፯፤ ቀን : ፳፫፤ ስዓትም : ይፈጽማል ::

፪፤፤ ሁለተኛ : ጵለኔታ : ዌኑስ : ነው :: እርሱም : ከከዋክብት : ሁሉ : ይዋባል :: ፀሓይን : በመውጣቱ : ሲቀድም : የጽዋት : ኮከብ : ይባላል :: በመግባቱም : ሲከተለው : የማታ : ኮከብ : ይሉታል :: ምልክቱም : ይህ : ነው :: ♀ :: መኻከለኛ : መስፈርያውም : ፯፯፵፫፤ ሚላ : ነው : ከፀሓይም : ፳፱፤ ሚልዮን : ሚላ : ይርቃል :: በ፪፳፬፤ ቀንም : ፲፯፤ ስዓትም : ፵፱፤ ደቂቅም : ፀሓይን : ይዞራል ::

፫፤፤ ምድርም : ሦስተኛ : ጵለኔታ : ናት :: ምልክትዋም : ይህ : ነው : ♁ :: ርቀትዋም : ከፀሓይ : ፲፫፤ ሚልዮን : ሚላ : ያህላል :: ፀሓይንም : በ፫፳፰ ቀን : ፰፤ ስዓ

ትም : ፶፮፡ ደቂቅም : ትዞራለች :: መኻከለኛ : መስፈርያ
ዋም : ፯፱፻፪፡ ሚላ : ነው :: ተከታይና : ባልንጀራም : አ
ላት : እርሱም : ጨረቃ : ነው :: እርሱም : ከምድር : ፳፬፡
አልፍ : ሚላ : ይርቃል :: መኻከለኛ : መስፈርያውም :
፪፻፲፪፡ ሚላ : ነው :: እርሱም : ምድርን : በ፳፯፡ ቀን : ፯፡
ስዓትም : ይዞራል : ብርሃኑ : ግን : በሥርዓት : በ፳፱፡ ቀን :
፲፪፡ ስዓት : ይለወጣል :: በሌህ : ፳፱፡ ቀን : በ፬፡ መልክ : አ
ናገኘዋለን :: በመጀመርያ : በፀሐይና : በምድር : መኻከ
ል : ሁኖ : የተጨለመውን : አኩሌታውን : ያሳየናል :: የ
ወር : መባቻ : መክንያት : ይህ : ነው :: ከዚያ : ወዲያም :
በጥቂት : በጥቂት : በልጦ : ወደ : ምሥራቅም : ሒደ : ወ
ደኛ : ያለውን : አኵሌታውን : በምዕራብ : ሲበራ : እናየ
ዋለን :: በኋላም : የበራውን : አኵሌታውን : ሁሉን : ያ
ሳየናል :: ከዚያ : ወዲያም : ለፀሐይ : ቀርቦ : ከኛ : ይመ
ለሳል :: ምድራችንም : በቅኝ : መንገድ : በጨረቃና : በፀ
ሐይ : መኻከል : ብትሆን : ጨረቃ : ትጨለምባታለች : የ
ምድር : ጽላ : በጨረቃ : ወድቋልና :: ይህ : የጨረቃ : ጨ
ለማ : ይባላል :: ጨረቃ : ግን : በምድርና : በፀሐይ : መኻ
ከል : ብትሆን : ይህም : በጨረቃ : መባቻ : ብቻ : ይገኛል :
ምድራችን : ተከፍላ : ትጨለምበታለች : የፀሐይም : ወ
ደስ : የምድር : ጨለማ : ይባላል ::

፬፡፡ አራተኛ : ጽለኔታ : ማርስ : ነው :: ምልክቱም : ይ
ህ : ነው : ♂ :: መኻከለኛ : መስፈርያውም : ፩፬፮፡፡ ሚላ ::
ርቀቱም : ከፀሐይ : ፻፶፬፡ ሚልዮን : ሚላ :: ሩጫውንም :
በ፮፹፮፡ ቀን : ፲፮፡ ስዓት : ፴፡ ደቂቅም : ይፈጽማል ::

፭፡፡ አምስተኛ : ጽለኔታ : ወስታ : ነው : ምልክቱም :
ይህ : ነው :: ⚴ :: ወስታም : ከሚቀሩ : ጽለኔቶች : ሁሉ :
ያንሳል :: መኻከለኛ : መስፈርያውም : ፫፻፡፡ ሚላ : ነ
ው :: ከፀሐይም : ፪፻፭፡ ሚልዮን : ሚላ : ይርቃል : ሩ
ጫውንም : በ፫፡ አመት : ፪፻፡፡ ቀንም : ፩፡ ስዓትም : ይፈ
ጽማል ::

፮፡፡ ስድስተኛ : ጽለኔታ : ዩኖ : ናት : ምልክትዋም : ይህ :
ነው :: ⚵ :: መኻከለኛ : ልክዋም : ፲፭፻፭፡ ሚላ : ነው : ከፀ

ሐይም ፡ ፪፻፶፡ ሚሊዮን ፡ ሚላ ፡ ትርቃለች ፡ በ፬፡ አመትም ፡ ፻፴፩፡ ቀንም ፡ ፲፡ ስዓትም ፡ ትዞረዋለች ፡፡

፯፡፡ ሰባተኛ ፡ ፕላኔታ ፡ ጰላስ ፡ ናት ፡ ምልክትዋም ፡ ይህ ፡ ነው ፡፡ ⚴ ፡፡ መኻከለኛ ፡ ልኳም ፡ ፪፪፻፭፡ ሚላ ፡፡ ርቀትዋም ፡ ከፀሐይ ፡ ፪፻፡ ሚሊዮን ፡ ሚላ ፡፡ በ፬፡ አመትም ፡ ፪፲፰፡ ቀንም ፡ ፰፡ ስዓትም ፡ ፀሐይን ፡ ትዞራለች ፡፡

፰፡፡ ኬሬስ ፡፡ ⚳ ፡፡ ርቀትዋ ፡ ከፀሐይ ፡ ፪፫፡፡ ሚሊዮን ፡ ሚላ ፡ ነው ፡፡ በ፬፡ አመትም ፡ ፪፲፱፡ ቀንም ፡ ፲፯፡ ስዓትም ፡ ፀሐይን ፡ ትዞራለች ፡፡ መኻከለኛ ፡ ልክዋም ፡ ፲፯፰፡፡ ሚላ ፡ ነው ፡፡

፱፡፡ ጁፒተር ፡፡ ♃ ፡፡ ከሁሉ ፡ የሚበልጥ ፡ ፕላኔታ ፡ ነው ፡፡ ልኩም ፡ ፹፱፰፻፡፡ ሚላ ፡ ነው ፡፡ ርቀቱም ፡ ከፀሐይ ፡ ፬፻፸፡ ሚሊዮን ፡ ሚላ ፡፡ ሩጫውንም ፡ በ፲፩፡ አመት ፡ ፫፻፲፩፡ ቀንም ፡ ፰፡ ስዓትም ፡ ፶፯፡ ደቂቅም ፡ ይፈጽማል ፡፡ እርሱም ፡ ፬፡ ተከታዮች ፡ ወይስ ፡ ጨረቆች ፡ አሉት ፡፡

፲፡፡ ሰቱርኑስ ፡፡ ♄ ፡፡ ለርሱ ፡ ታላቅ ፡ ሁለተኛም ፡ ቀለበት ፡ አለው ፡ የሚዞረው ፡ ፯፡ ተከታዮችም ፡፡ እርሱም ፡ ፱፻፰፡ ሚሊዮን ፡ ሚላ ፡ ከፀሐይ ፡ ይርቃል ፡ ሩጫውንም ፡ በ፳፱፡ አመት ፡ ፻፷፰፡ ቀንም ፡ ፲፱፡ ስዓትም ፡ ፶፩፡ ደቂቅም ፡ ይፈጽማል ፡ ልኩም ፡ ፸፱፯፻፡፡ ሚላ ፡ ነው ፡፡

፲፩፡፡ ኋለኛ ፡ ፕላኔታ ፡ ኡረኖስ ፡ ነው ፡፡ ♅ ፡፡ እርሱም ፡ ፲፰፲፯፡ ሚሊዮን ፡ ሚላ ፡ ከፀሐይ ፡ ርቆ ፡ ሩጫውን ፡ በ፹፫፡ አመት ፡ ፻፶፡ ቀንም ፡ ፲፰፡ ስዓትም ፡ ይፈጽማል ፡ ልኩም ፡ ፴፱፱፻፡፡ ሚላ ፡ ነው ፡ ፯፡ ተከታዮችም ፡ ተገኝተውበታል ፡፡

---

## ስለ ፡ ምድር ፡ መልክ ፡፡

የምድር ፡ መልክ ፡ በሁለት ፡ መውጫዋ ፡ በሰሜንና ፡ በደቡብ ፡ ጥቂት ፡ ትጉድላለች ፡ እንጅ ፡ ክብ ፡ ናት ፡ አረርንም ፡ ትመስላለች ፡፡




የምድርም ፡ ክብነት ፡ ከዚህ ፡ ይገለጻል ፡፡ ፩፡፡ የምድር ፡ ጽላ ፡ በጨረቃ ፡ ቢታይ ፡ ክብ ፡ ነው ፡፡ ፪፡፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ የፀሓይ ፡ መውጣትና ፡ መግባት ፡ ይቀድማቸዋል ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ ከሚኖሩ ፡ በፊት ፡፡ ፫፡ የከዋክብት ፡ ሁሉ ፡ መልክ ፡ አረርን ፡ ይመስላል ፡፡ ፬፡፡ በምድር ፡ ከፍ ፡ በሚል ፡ ስፍራ ፡ ብንወጣ ፡ ማየታችን ፡ ይስፋል ፡ በመውጣታችን ፡ መጠን ፡፡ ፭፡፡ ማየታችን ፡ በሌላ ፡ ነገር ፡ ባይከለከል ፡ የምናየው ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ክብ ፡ ሁኖ ፡ ይታያል ፡፡ ፮፡ ካመት ፡ ፲፭፻፲፱፡፡ ጀምሮ ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ምድ

ርን ፡ በመርከብ ፡ ሰረው ፡ ዞርዋት ፡፡ የሰረረትንም ፡ መንገ
ደቸውን ፡ አቀንተው ፡ ወደ ፡ ፊታቸው ፡ ሲሔዱ ፡ ሳይለው
ጡትም ፡ በመጨረሻ ፡ ወትረ ፡ ወደ ፡ ጀመረበት ፡ ስፍራ ፡
ደረሱ ፡፡ ፲፩ ወደ ፡ ባሕር ፡ ከሚሔዱ ፡ መርከቦች ፡ ላይን ፡
በመጀመርያ ፡ የሚጠፋ ፡ ነገር ፡ የታችኛ ፡ መርከብ ፡ ነው ፡
በኋላም ፡ ደክሎች ፡ ይጠፋሉ ፡፡ ከሚመጡም ፡ መርከቦ
ች ፡ ደክሎች ፡ በፊት ፡ ይታያሉ ፡ መርከቦችም ፡ በኋላ ፡፡

## የምድር ፡ መኻከለኛ ፡ ልክ ፡፡ ዞዲያኮስ ፡፡ የምላሽ ፡ ዙርያ ፡፡ ሖሪዞን ፡፡ ፬ ማዕዝን ፡፡ አርዞች ፡፡

ምድርን ፡ በመዞር ፡ የፊትዋ ፡ ታላቅነት ፡ ተገኘ ፡፡ ዙርያዋ
ም ፡ ፶፬ ሺህ ፡ ፱፻፩ ሚላ ፡ ነው ፡፡ ይህም ፡ ለግረኛ ፡ መንገ
ድ ፡ ከሆነ ፡ የሺህ ፡ ተስማንያ ፡ ቀን ፡ መንገድ ፡ ቢሆን ፡፡ የ
ምድርም ፡ መኻከለኛ ፡ ልክ ፡ ፲፱፻፫ ሚላ ፡ ያህላል ፡፡ ምድ
ርም ፡ ያለ ፡ መለወጥ ፡ በየ፳፬ ሰዓት ፡ ከምዕራብ ፡ ወደ ፡
ምሥራቅ ፡ አድርጋ ፡ በራስዋ ፡ ትዞራለች ፡ እንዲሁም ፡ ቀን
ና ፡ ሌሊት ፡ ይሆናሉ ፡፡ ምድር ፡ ደግሞ ፡ ባንድ ፡ አመት ፡ ከ
ጨረቃ ፡ ጋራ ፡ ፀሓይን ፡ ትዞራለች ፡፡ ምድርም ፡ እንዲህ ፡ ስ
ትዞር ፡ ፀሓይ ፡ የሚዞር ፡ ይመስላል ፡ በውነት ፡ ግን ፡ ምድ
ር ፡ ትዞራለች ፡፡

ፀሓይም ፡ እንዲህ ፡ ዙሮ ፡ ሲመስል ፡ ፲፪ የከዋክብትን ፡
ምልክቶች ፡ ዞዲያኮስ ፡ የሚሉትን ፡ ያልፋል ፡፡ እርሳቸው
ም ፡ እሌህ ፡ ናቸው ፡፡

ሚዛን ፡፡ ♎ ፡፡ ጊንጥ ፡፡ ♏ ፡፡ ወርዋሪ ፡፡ ♐ ፡፡ ቀላ ፡፡ ♑ ፡፡
ወኃዊ ፡፡ ♒ ፡፡ ዓሦች ፡፡ ♓ ፡፡ ደንገሌ ፡፡ ♈ ፡፡ ወይፈን ፡፡ ♉ ፡፡
መንታ ፡፡ ♊ ፡፡ ከንክር ፡፡ ♋ ፡፡ አንበሳ ፡፡ ♌ ፡፡ ቀንጆ ፡፡ ♍ ፡፡
ፀሓይም ፡ ወደ ፡ ከንክር ፡ ምልክት ፡ ሲገባ ፡ በኛ ፡ በኩል ፡
ቀን ፡ ይረዝማል ፡ በምድር ፡ ሁለተኛ ፡ እኩሌታ ፡ ግን ፡ ያ
ጽራል ፡፡ ወደ ፡ ቀላም ፡ ምልክት ፡ ሲገባ ፡ የኩሌታችን ፡ ቀ
ን ፡ ያጽራል ፡ የሁለተኛ ፡ እኩሌታ ፡ ቀን ፡ ግን ፡ ይረዝማል ፡፡
በሌህ ፡ ሁለት ፡ ምልክቶች ፡ ፀሓይ ፡ ገብቶባቸው ፡ መመለ
ስ ፡ ይመስላልና ፡ ይህ ፡ የፀሓይ ፡ ምላሽ ፡ ይባላል ፡፡ በም
ላሽም ፡ በኩል ፡ ያለ ፡ የምድር ፡ ዙርያ ፡ የመላሽ ፡ ዙር
ያ ፡ ይባላል ፡፡ ከርሳቸውም ፡ አንዱ ፡ የከንክር ፡ ምላሽ ፡

ዙርያ : ነው : አንዲም : የዋላ : ምላሽ : ዙርያ ::

ክፍ : በሚል : ስፍራ : ላይ : ብንቆም : ሰማይ : ከሩቅ : ክብ : ሁኖ : ምድርን : የሚወስን : ይመስላል :: ይህም : የማየት : ዙርያ : ወይስ : ሖሪዞን : ይባላል :: እኛም : በመኻከሉ : ነን :: ይህም : በ፫፻፷ በተካከሉ : ክፍሎች : ይከፈላል : አርዝ : ኢየተባሉ :: ከዚህ : መክፈልም : በቀር : ሖሪዞን : ደግሞ : በአራት : ክፍል : ይከፈላል :: እርሳቸውም : ያለም : ወይስ : የሰማይ : ፬ ማዕዝንት : ይባላሉ : ስማቸውም : ምሥራቅ : ምዕራብም : ሰሜንም : ደቡብም :: ክፍልም : ሁሉ : ከየባልንጀራው : ፺ አርዝ : ይርቃል :: እሌህ : ፬ ክፍሎች : ደግመው : ይከፈላሉ : በመርከቦችም : ፳፬ ክፍል : አላቸው : መንገዳቸውንና : ንፋሳቸውን : በጣም : ያውቁበት : ዘንድ : ብለው :: ይህ : መክፈልም : ከመግኔትስ : መርፌም : ጋራ : የተገኘበት : አቃ : ዲር : ይባላል :: ለመርከብም : ለመንገደኛም : እንደ : መሪ : ያገለግላል ::

የምድር : አረር : አስተካካይ : በሚሉት : መስምር : በሁለት : እኩሌቶች : ይከፈላል :: አንዲቱም : የሰሜን : እኩሌታ : አንዲቱም : የደቡብ : እኩሌታ : ናት :: አስተካካይ : በሰሜንና : በደቡብ : መኻከል : ረጥዋልና : ፪ እኩሌቶች : በጣም : የተካከሉ : ይሆናሉ :: ከርሱም : ጋራ : በሰሜንና : በደቡብ : በኩል : አያሌ : መስምሮች : አሉ : እንደርሱ : የሚርጡ : እርሳቸውም : ጳራሌል : ዙርያ : ይባላሉ :: እንዲሁም : የከንክርና : የዋላ : ምላሽ : ዙርያ : የመውጫም : ፪ ዙርያ :: የምላሽም : ዙርያ : ኢያንደንዱ : ፻፹ አርዝ : ተኩል : ካስተካካይ : ይርቃል :: አስተካካይ : ግን : ከጳራሌል : ዙርያ : ሁሉ : ጋራ : መረዲያኖች : በሚባሉ : ከሰሜን : ወደ : ደቡብ : በሚርጡ : መስምሮች : ቀንተው : ይቈረጣሉ :: መሪዲያንም : ሁሉ : በየስፍራው : ምድርን : በምሥራቅና : በምዕራብ : ይከፍላል ::

## የምድር : ወርድና : ርዝመት ::

የስፍራ : ሁሉ : ርቀት : ካስተካካይ : ወደ : ሰሜን : ወይስ : ወደ : ደቡብ : ወርድ : ይባላል :: ርቀቱም : ከመጀመር

ያ ፡ መሪደ.ያን ፡ ርዝመቱ ፡ ነው ፡፡ የስፍራም ፡ ወርድ ፡ ካስ
ተካካይ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ቢኖር ፡ የሰሜን ፡ ወርድ ፡ ይባላ
ል ፡፡ ወደ ፡ ደቡብም ፡ ቢኖር ፡ የደቡብ ፡ ወርድ ፡ አለው ፡፡ የ
ወርድም ፡ አርዝ ፡ ሁሉ ፡ በመሪደ.ያን ፡ ይቈጠራል ፡፡ የርዝ
መትም ፡ አርዝ ፡ ባስተካካይ ፡፡ የመውጫ ፡ ክፍታ ፡ ባን
ድ ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡ የስፍራ ፡ መውጫ ፡ ክፍታ ፡ ይባላል ፡ እ
ርሱም ፡ ከወርደ. ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ፡፡ ካንድ ፡ መሪደ.ያ
ን ፡ በታች ፡ ያለ ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ ርዝመቱና ፡ ቀትሩ ፡ አን
ድ ፡ ነው ፡፡

## የምድር ፡ ዞና ፡ ወይስ ፡ መታጠቅያ ፡፡

ምድር ፡ በፀሐይ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ በምትኖር ፡ መጠን ፡ ባም
ስት ፡ ዞና ፡ ወይስ ፡ መታጠቅያ ፡ በሚሉት ፡ ክፍል ፡ ትከ
ፈላለች ፡፡ የምድርን ፡ አረር ፡ እንደ ፡ መታጠቅያ ፡ ከብዋታ
ልና ፡፡ በሁለት ፡ ምላሽ ፡ ዙርያ ፡ መኻከል ፡ ያለች ፡ ምድ
ር ፡ ሁሉ ፡ ትኵስ ፡ ዞና ፡ ትባላለች ፡፡ የፀሐይ ፡ ብልጭታ ፡
በራስዋ ፡ ላይ ፡ ጶርጶንደ.ኩላሪተር ፡ ቀንቶ ፡ ይወድቅባታል
ና ፡፡ ፀሐይም ፡ እጅግ ፡ ተኵሶባታልና ፡፡ የዚህም ፡ ዞና ፡ ወ
ርድ ፡ ፵፯፡ አርዝ ፡ ነው ፡፡ በየመውጫና ፡ በየመውጫ ፡ ዙ
ርያ ፡ መኻከልም ፡ ያለ ፡ ስፍራ ፡ የውርጭ ፡ ዞና ፡ ይባላል ፡፡
ፀሐይ ፡ ካጠገቡ ፡ አድርጎ ፡ ኦብሊኩተር ፡ ያበራዋልና ፡ አያ
ሞቀውምም ፡፡ በየብርድና ፡ በትኵስ ፡ ዞና ፡ መኻከልም ፡
ወደ ፡ ሰሜንና ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ አንድ ፡ መኻከለኛ ፡ የሚባ
ል ፡ ዞና ፡ [illegible] ፡ ትኵሳትና ፡ ብርድ ፡ በርሱ ፡ መኻከለኛ ፡ ነ
ውና ፡ እንደሁም ፡ የምድር ፡ ትኵሳትና ፡ ብርድ ፡ ይበዛል
ና ፡ ያንሳል ፡፡ ቀንና ፡ ሌሊትም ፡ ያጽራልና ፡ ይረዝማል ፡፡ በ
ትኵስ ፡ ዞና ፡ የቀንና ፡ የሌሊት ፡ ርዝመት ፡ ጥቂት ፡ ይለያ
ል ፡ እንጂ ፡ አንድ ፡ ነው ፡ ባመት ፡ ሁላንትና ፡፡ በመኻከለ
ኛ ፡ ዞናም ፡ ቀንና ፡ ሌሊት ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ያጽራሉ ፡ አንድ ፡
ጊዜም ፡ ይረዝማሉ ፡፡ በየመውጫ ፡ በኵልም ፡ ከሁሉ ፡ የ
ሚረዝም ፡ ቀን ፡ ፯፡ ወር ፡ ይኖራል ፡፡ ከሁሉም ፡ የምትረ
ዝም ፡ ሌሊት ፡ ፯፡ ወር ፡፡

ይህ ፡ ነገርም ፡ ሁሉ ፡ ግሎቡስ ፡ በሚሉት ፡ በምድር ፡ ም
ሳሌ ፡ ይገኛል ፡፡

## ሁለተኛ ፡ ክፍል ፡፡

## ጊዎግራፊያ ፡ ፊሲቂ ፡፡

ጊዎግራፊያ ፡ ፊሲቂ ፡ የምድርን ፡ ፊሲስ ፡ ማለት ፡ ጠባይዕ ፡ ታስተምረናለች ፡ መሬቱንም ፡ ተራራውንም ፡ ውኃውንም ፡ ፈሬውንም ፡ ታስታውቀናለች ፡፡

### የምድር ፡ አረር ፡፡

ከምድር ፡ አረር ፡ ፊቱን ፡ ብቻ ፡ ተከፍሎ ፡ እናውቃለን ፡ በውሥጡ ፡ ያለውን ፡ ግን ፡ አናውቅም ፡፡ በምድር ፡ ፊትም ፡ ድርቅ ፡ ምድር ፡ ከውኃ ፡ ተለየ ፡፡ ውኃውም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ዝቅ ፡ በሚል ፡ ስፍራ ፡ ተከማችትዋል ፡፡ የምድር ፡ ፊት ፡ ታላቅ ፡ ጥልቅ ፡ የውኃም ፡ ሁሉ ፡ መሰብሰቢያ ፡ ባሕር ፡ ነው ፡፡ ደርቅ ፡ ምድርን ፡ ሁሉን ፡ የሚዞር ፡ ታላቅ ፡ ባሕር ፡ ያለም ፡ ባሕር ፡ ይባላል ፡ በዮናኒ ፡ ቋንቋም ፡ ዎቅያኖስ ፡፡ የድርቅ ፡ ምድርም ፡ ታላቅ ፡ መስብሰቢያ ፡ ሁሉ ፡ ኮንቲነንት ፡ ይባላል ፡ ወይስ ፡ የምድር ፡ ክፍል ፡፡ የምድር ፡ ክፍሎችም ፡ ፭፤ ናቸው ፡ እርሳቸውም ፡ ኤውሮጳ ፡ እስያም ፡ አፍሪካም ፡ አሜሪካም ፡ ኣውስትራልያም ፡፡ በምድር ፡ ፊት ፡ ውኃ ፡ ይበዛል ፡ ድርቅ ፡ ምድርም ፡ ያንሳል ፡፡ ደርቅ ፡ ምድር ፡ ፩/፫ ፡፡ ውኃ ፡ ግን ፡ ፪/፫ ፡ ነው ፡፡

### በደርቅ ፡ ምድር ፡ ስላሉ ፡ ስለ ፡ ተራሮችና ፡ ስለ ፡ ሌላ ፡ ነገር ፡፡

ማናቸይቱ ፡ ምድር ፡ ተራራ ፡ ባይገኝባት ፡ ወይስ ፡ ታና[illegible] ፡ ኮረፍታ ፡ ብቻ ፡ ቢገኝባት ፡ ሜዳ ፡ ትባላለች ፡፡ ከፍ ፡ የሚልም ፡ የምድር ፡ ስፍራ ፡ ብቻውን ፡ የሚኖር ፡ ተራራ ፡ ይባላል ፡፡ አያሌ ፡ ተራሮችም ፡ ባንድ ፡ ቢገኙ ፡ የተራሮች ፡ መሰብሰቢያ ፡ ወይስ ፡ የተራሮች ፡ ሰንስለት ፡ ወይስ ፡ የተራሮች ፡ ተርታ ፡ ይልዋቸዋል ፡፡ በተራሮች ፡ መኻከልም ፡ ያለች ፡ ምድር ፡ ወይስ ፡ ሜዳ ፡ ወይስ ፡ ቆላ ፡ ይልዋታል ፡፡ ታላቅ ፡ ብትሆንም ፡ ድንገትም ፡ ወደ ፡ ታች ፡ ብትወርድ ፡ ቊልቊለት ፡ ወይስ ፡ ጉድጓድ ፡ ትባላለች ፡፡ ከ

ምድር ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ የሚወጣ ፡ ጥቂት ፡ ከፍ ፡ የሚልም ፡ ምድር ፡ ካ ጵ ፡ ማለት ፡ ራ.ስ ፡ ይባላል ፡፡ የምድር ፡ ከፍታ ፡ ሁሉ ፡ በባሕር ፡ ፊት ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ በሚል ፡ መጠን ፡ ይሰፈ ራል ፡፡ ከፍ ፡ የሚልም ፡ የተካከለም ፡ ምድር ፡ ወርዱ ፡ የ ማይበዛ ፡ የ ምድ ር ፡ ጀ ር ባ ፡ ይባላል ፡፡ ታላቅም ፡ ሰፊም ፡ ቢሆን ፡ የ ከ ፍ ታ ፡ ሜ ደ ፡ ወይስ ፡ ጵ ላ ቶ ፡ ይባላል ፡፡ ም ድርም ፡ ከጵላቶ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ በጥቂት ፡ በጥቂትም ፡ የም ትወርድ ፡ የ ጵ ላ ቶ ፡ ጠ ፈ ር ፡ ትባላለች ፡፡ ከሁሉ ፡ የሚበ ልጡ ፡ ጵላቶች ፡ በደቡብ ፡ አሜሪካና ፡ በመኻከለኛ ፡ እስ ያ ፡ በአፍሪካም ፡ ይገኛሉ ፡፡ እሌህም ፡ ባሽዋ ፡ በረኾች ፡ ና ቸው ፡ እልያ ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ፍርያም ፡ ናቸው ፡፡

የሚጠቅሙም ፡ ሚነራሎች ፡ የውኃ ፡ ምንጮችም ፡ የጭ ውና ፡ የጤና ፡ ምንጮችም ፡ ሁሉ ፡ በተ ራ.ሮ ች ፡ ይገኛሉ ፡፡ ተራ.ሮችም ፡ በ፫ ፡ ይከፈላሉ ፡፡ የሚቀድሙ ፡ ተራ.ሮች ፡ መ ኻከለኞችም ፡ አይነተኞችም ፡ ተራ.ሮች ፡፡ የሚቀድሙም ፡ ተራ.ሮች ፡ ታናሾች ፡ ናቸው ፡፡ መኻከለኞችም ፡ ከርሳቸው ፡ ጥቂት ፡ ይበልጣሉ ፡፡ በሌህ ፡ ሁለትም ፡ ከድር ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ እጅግ ፡ መለዋወጥ ፡ ሆነባቸው ፡፡ ከርሳቸው ፡ የ ሚበልጡ ፡ አይነተኞች ፡ ተራ.ሮች ፡ የመጀመርያ ፡ ተራ.ሮች ፡ ይባላሉ ፡ ከጥንትም ፡ ጥቂት ፡ መለወጥ ፡ የሆነባቸው ፡ ይ መስላሉ ፡፡ በርሳቸውም ፡ የተገኘ ፡ የግ ራ.ኒ ት ፡ ደንጊያ ፡ ብርቱ ፡ ነው ፡፡ ሁለት ፡ ታላላቆች ፡ ተራ.ሮች ፡ አሉ ፡ አን ዲም ፡ ሺ ም ቦ ረ ሶ ፡ በደቡብ ፡ አሜሪካ ፡ ከፍታውም ፡ ፳፬፻፵፬፡ አግር ፡ ነው ፡ ወይስ ፡ ፲፬፡ ሽህ ፡ ፪፡ መቶ ፡ ፺፬፡ ክን ድ ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡፡ ሁለተኛም ፡ ደ ወ ለ ጊ ር ፡ በስያ ፡ ነው ፡ ከፍታው ፡ ፳፫፻፳፫፡ አግር ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡ ያለ ፡፡ አያሌ ፡ ተራ.ሮችም ፡ አንደንድ ፡ ጊዜ ፡ እሳትን ፡ ይተፋሉ ፡ ው ል ካ ኖ ችም ፡ ይባላሉ ፡፡ የምድር ፡ መናወጽም ፡ ከሳትና ፡ ከው ኃ ፡ የተነሣ ፡ ይመስላል ፡፡ ብዙ ፡ ከፍ ፡ ያሉ ፡ ተራ.ሮች ፡ ወ ትሩ ፡ ውርጭንና ፡ በረደን ፡ ይለብሳሉ ፡፡ በተራ.ሮች ፡ ውሥ ጥም ፡ አያሌ ፡ ጊዜ ፡ ዋሾች ፡ ይገኛሉ ፡፡ ሁለት ፡ ኮንቲነንቶ ችን ፡ ባንድ ፡ የምታገናኛቸው ፡ በሁለት ፡ ባሕሮችም ፡ መኻ ከል ፡ የምታልፍ ፡ ጸቢብ ፡ ምድር ፡ ኢስትሞስ ፡ ትባላለ

ች ፡፡ እጅግም ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ የምትገባ ፡ ጸቢብ ፡ ምድር ፡ የምድር ፡ ምላስ ፡ ትባላለች ፡፡

## በደርቅ ፡ ምድር ፡ ስላሉ ፡ ፈሳሾችና ፡ ባሕሮች ፡ ስለ ፡ ሌሎች ፡ ውኆችም ፡፡

የደርቅ ፡ ምድር ፡ ውኆች ፡ ምንጮች ፡ ፈሳሾችም ፡ ወንዞችም ፡ መስኖችም ፡ ባሕሮችም ፡ ናቸው ፡፡ እሊህም ፡ ከጭው ፡ ባሕር ፡ ለመለየት ፡ የምድር ፡ ባሕሮች ፡ ይባላሉ ፡፡ ከሁሉ ፡ የሚበልጡ ፡ የምድር ፡ ባሕሮች ፡ የከስጲያ ፡ ባሕር ፡ በሩስያ ፡ መንግሥት ፡ የከነደ ፡ ባሕሮችም ፡ ባሜሪካ ፡ ናቸው ፡፡ መናቸው ፡ ምንጭ ፡ ሲወጣ ፡ ታናሽ ፡ ፈሳሽ ፡ ይሆናል ፡፡ ብዙ ፡ ፈሳሾችም ፡ ባንድ ፡ ሲገናኙ ፡ ወንዝ ፡ ይሆናል ፡፡ ፈሳሽ ፡ ወይስ ፡ ወንዝ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ወንዝ ፡ ወይስ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ወደሚገባበት ፡ ስፍራ ፡ የፈሳሽ ፡ ወይስ ፡ የወንዝ ፡ አፍ ፡ ይባላል ፡ የሚያልፍባትም ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ግዛቱ ፡ ትባላለች ፡፡ ወንዝ ፡ ከታላቅ ፡ ከፍታ ፡ ድንገት ፡ ወደ ፡ ታች ፡ ቢወርድ ፡ የወንዝ ፡ ፏዋፏዋቴ ፡ ወይስ ፡ ከተረክት ፡ ይሆናል ፡፡ ሁለት ፡ ወንዞችን ፡ ባንድ ፡ የሚገጥም ፡ ውኃ ፡ መስኖ ፡ ይባላል ፡፡ ከምንጮችም ፡ አያሌ ፡ አሉ ፡ አንደንድ ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ፡ የሚፈሉ ፡፡ አያሌም ፡ የሚነራል ፡ ምንጮች ፡ ናቸው ፡፡ ከርሳቸውም ፡ ብዙ ፡ ለጤና ፡ ያገለግላሉ ፡ ብዙ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ሕማም ፡ ተሽሮባቸዋልና ፡፡

## ዎቅያኖስ ፡ ታላቅ ፡ ባሕር ፡፡

በፅርዕ ፡ ቋንቋ ፡ ዎቅያኖስ ፡ የሚሉት ፡ ታላቅ ፡ ባሕር ፡ ደርቅ ፡ ምድርን ፡ ሁሉን ፡ ይዞራል ፡፡ ጥልቁም ፡ ባንደንድ ፡ ስፍራ ፡ ፰፣ ሚላ ፡ ያህላል ፡፡ በውሥጡም ፡ ሚደና ፡ ተራራ ፡ ደንጊያም ፡ አታክልትም ፡ አለ ፡፡ ከውኃ ፡ በላይ ፡ የሚወጡ ፡ ተራሮች ፡ ደሴቶች ፡ ይባላሉ ፡፡ ዎቅያኖስም ፡ በ፭፣ ታላቅ ፡ ክፍል ፡ ይከፈላል ፡ እርሳቸውም ፡ እሊህ ፡ ናቸው ፡ የሰሜን ፡ ውርጭ ፡ ባሕር ፡፡ የምዕራብም ፡ ዎቅያኖስ ፡ አትለንቲስ ፡ የሚባል ፡ የህንድም ፡ ዎቅያኖስ ፡፡ የምሥራቅም ፡ ወይስ ፡ የጸጥታ ፡ ዎቅያኖስ ፡፡ የደቡብም ፡ ውርጭ ፡ ባሕር ፡፡ ቍጥርም ፡ ከሌለው ፡ ከታናሾች ፡

ፈሳሾች ፡ በቀር ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ የሚፈሱ ፡ ከ፷፱፡፡ የሚበዙ ፡ ታላቆች ፡ ወንዞች ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ይገባሉ ፡፡ ወደ ፡ ባሕርም ፡ የሚገባ ፡ ውኃ ፡ ሁሉ ፡ ይጻፈጣል ፡ የባሕር ፡ ውኃ ፡ ሁሉ ፡ መራራና ፡ ጨው ፡ ነው ፡፡ ባንደንድ ፡ ስፍራም ፡ የባሕር ፡ ውኃ ፡ በሌሊት ፡ ያበራል ፡፡ ከባሕርም ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ጉም ፡ ሁኖ ፡ የሚወጣ ፡ ውኃ ፡ በደመና ፡ ይሰበሰባል ፡ ንፋስም ፡ ወደ ፡ ደርቅ ፡ ምድር ፡ ይወስደዋል ፡ በኋላም ፡ ዝናም ፡ ሁኖ ፡ በረደም ፡ ሁኖ ፡ ውርጭም ፡ ሁኖ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ይዘንማል ፡፡ ባሕርም ፡ በየጊዜው ፡ ይነሣልና ፡ ይወድቃል ፡፡ በብዙ ፡ ስፍራም ፡ ይህ ፡ በየስድስት ፡ በሌላ ፡ ስፍራም ፡ በያራት ፡ ስዓት ፡ ነው ፡ ይህም ፡ በእንግሊዝ ፡ ቋንቋ ፡ ተ ይ ድ ስ ፡ ይባላል ፡፡ የተይድስም ፡ መክንያት ፡ ጨረቃና ፡ ፀሓይ ፡ ነው ፡፡ ንፋስ ፡ ባይኖር ፡ የባሕር ፡ ፊት ፡ ጸጥ ፡ ይላል ፡ መስተወትንም ፡ ይመስላል ፡ ንፋስ ፡ ግን ፡ ሞገድን ፡ ያስነሣል ፡፡ አውሎ ፡ ንፋስም ፡ ታላቅ ፡ ቤት ፡ የሚመስልን ፡ ሞገድ ፡ ያስነሣል ፡፡ ባንደንድ ፡ ስፍራ ፡ መደ ፡ አለ ፡ በባሕር ፡ በየጊዜው ፡ ወደስ ፡ ወትሩ ፡ መርከቦችን ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ የሚወስድ ፡፡ አንደንድ ፡ ስፍራም ፡ አለ ፡ ውኃው ፡ የሚዞርበት ፡፡ መርከብም ፡ ወደዚያ ፡ ቢቀርብ ፡ ውኃ ፡ ወደ ፡ ታች ፡ ይወስደዋል ፡ መደንም ፡ የለም ፡፡ በባሕር ፡ ደርቻ ፡ በብዙ ፡ ስፍራ ፡ ባሕር ፡ ወደስ ፡ እጅግ ፡ ወደስ ፡ ጥቂት ፡ ወደ ፡ ደርቅ ፡ ምድር ፡ ይገባል ፡ ያም ፡ ስፍራ ፡ ጉበት ፡ ይባላል ፡ ወደስ ፡ ቤይ ፡፡ ከዚያም ፡ መርከቦች ፡ ያርፋሉ ፡ መርስንም ፡ ወደስ ፡ ሚናን ፡ ያገኛሉ ፡፡ በዙርያዋ ፡ ሁሉ ፡ ውኃ ፡ ያላት ፡ ምድር ፡ ደሴት ፡ ናት ፡፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ ግን ፡ ከኮንቲነንት ፡ ጋራ ፡ ብትገጠም ፡ ጴኒንሱላ ፡ ትባላለች ፡፡ ብዙ ፡ ደሴቶችም ፡ ባንድ ፡ ቢገኙ ፡ አርኪጴላጎስ ፡ ይባላሉ ፡፡

## አየር ፡፡ አትሞስፌራም ፡፡ ሜቲዎርም ፡፡ ንፋሳትም ፡ ትኩሳትና ፡ ብርድም ፡፡

ያ ፡ ረቂቅ ፡ ማየትንም ፡ የሚያሳልፍ ፡ ከቢድም ፡ አለስቲቁም ፡ ነገር ፡ ወትሩ ፡ የምንነፍሰው ፡ ባካላችንም ፡ ሰምተን ፡ የማናየው ፡ አየር ፡ ነው ፡፡ የሚከበነም ፡ ያየር ፡ ክፍ

ል ፡ የውኃና ፡ የምድር ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ ወዝ ፡ ጢስም ፡ እ
ስተንፈስም ፡ የሚገባበት ፡ አትሞስፌሬ ፡ ይባላል ፡ እር
ሱም ፡ ያየር ፡ ሦስት ፡ ደርብ ፡ ናቸው ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡
የተለዩ ። ታችኛ ፡ ደርብም ፡ የሞቀ ፡ ነው ። ሁለተኛ ፡ ደርብ
ም ፡ ብርድ ፡ ነው ፡ የበረደ ፡ የውርጭመ ፡ ስፍሬ ። በታቹ ፡
ውኃ ፡ የነበረ ፡ በላይ ፡ ይረጋልና ። ሦስተኛ ፡ ደርብም ፡ ከሁ
ሉ ፡ ይልቅ ፡ ይበርዳል ። ባትሞስፌሬም ፡ ያለ ፡ ሁሉ ፡ የሚ
ታይም ፡ ሜቴዎር ፡ ይባላል ፡ እንዲሁም ፡ ጉም ፡ ጸጋግም ፡
ደመናም ፡ ዝናምም ፡ የዝናም ፡ ቀስትም ፡ የደመና ፡ ፍሬ
ሽም ፡ ጉርፍም ፡ የመሬት ፡ ኩርፌትም ፡ የውኃ ፡ ኩርፌት
ም ። ሁለተኛ ፡ ፀሓይም ፡ ሁለተኛ ፡ ጨረቃም ፡ መጽባትና ፡
መሸትም ፡ በረድም ፡ መብረቅም ፡ ነጐደጓድም ፡ የሰሜን
ና ፡ የደቡብ ፡ ብርሃንም ፡ የሳት ፡ አረርም ፡ የከዋክብት ፡ መ
ወርወርም ፡ ነፋሳትም ፡ የሚቀርም ። ያየር ፡ ክብድ ፡ ቢለ
ወጥ ፡ ሚዛኑም ፡ ባይከከል ፡ አየር ፡ ተናውጥዋልና ፡ ነፋስ ፡
ይሆናል ። በየጊዜያቸው ፡ የሚለወጡ ፡ ነፋሳት ፡ እሌህ ፡
ናቸው ፡ በመላሽ ፡ ዙርያ ፡ በኩል ፡ የሚነፍሱ ፡ የጸሳት ፡
ነፋሳት ፡ በህንድ ፡ ባሕርም ፡ መውሱን ፡ የሚባል ፡ ነፋስ ፡
በየ፯፡ ወር ፡ የሚለወጥ ። በየጊዜያቸውም ፡ ያሉ ፡ የባሕር
ና ፡ የምድር ፡ ነፋሳት ፡ የምሥር ፡ ኸምሲን ፡ የፈርስም ፡
ሰሙም ፡ የምዕራብ ፡ አፍሪካ ፡ ሀርመታንም ፡ የኢጣልያ ፡
ሺሮኮም ፡ እንዲህ ፡ ናቸው ።

ትኩሳትና ፡ ብርድ ። በየዞና ፡ የምድር ፡ ተኩሳትና ፡
ብርድ ፡ ይለያል ። በባሕር ፡ ደርም ፡ በምድር ፡ መኻከልም ፡
ያለ ፡ ከፍ ፡ የሚልና ፡ ዝቅ ፡ የሚልም ፡ እጅግ ፡ የሚተከል
በትም ፡ የማይተከልበትም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ በሙቀት ፡ እር
ሱ ፡ በርሳቸው ፡ ይለያሉ ።

ፊሲቄ ፡ ጽሮጌኔ ። ፊሲቄ ፡ ጽሮጌኔ ፡ ማለት ፡ ሁሉ ፡ ነው ፡
ከባሕርና ፡ ከምድር ፡ በሰው ፡ እጅ ፡ ወይስ ፡ እንዲያው ፡ የ
ሚወጣ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ። የብልሃት ፡ ጽሮጌኔ ፡ ማለት ፡ ከሰ
ው ፡ ብልሃትና ፡ ስራ ፡ የሚወጣ ። ፊሲቄ ፡ ጽሮጌኔ ፡ ከ፫፡ ከ
ፍጥረት ፡ መንግሥቶች ፡ ይወጣል ። ከሚኔራል ፡ ወይስ ፡ ደ
ንጊያ ፡ መንግሥት ፡ ካታክልትም ፡ መንግሥት ፡ ከንስሮች

ም ፡ መንግሥት ፡፡ ሚነራሎችንም ፡ ባሬት ፡ ክፍል ፡ ይከፈ
ላሉ ፡፡ ፩፡ የመሬትና ፡ የደንጊያ ፡ ወገን ፡፡ ፪፡፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡
ጭው ፡ ወገን ፡፡ ፫፡፡ የ ሚ ነ ደ ፡ ሚነራሎች ፡፡ ፬፡፡ ሜታሎች ፡፡
ከሜታሎችም ፡ አሁን ፡ ፳፰፡ ልዩ ፡ አይነት ፡ ተገኙ ፡፡ ያታክል
ትም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ አይነት ፡ አሁን ፡ ፵፲፱፡፡ ታወቁ ፡ የንስሶች
ም ፡ ፳፲፱፡፡ ልዩ ፡ አይነት ፡፡

## ስለ ፡ ሰው ፡፡

ምድራችን ፡ ለሰው ፡ ማደርያ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ተፈጠረ
ች ፡፡ እርሱም ፡ በምድር ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ምስጋና ፡ ያይ ፡
ዘንድ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ በሁሉ ፡ ያመሰግን ፡ ዘንድ ፡ ነበ
ር ፡፡ ሰውም ፡ በኀጢአት ፡ ሳይወድቅ ፡ በምድር ፡ የታድላ ፡ ገ
ነት ፡ ነበረ ፡፡ በኀጢአት ፡ ግን ፡ ከወደቀ ፡ በኋላ ፡ ፍጥረት
ም ፡ ከጥፋት ፡ መርገም ፡ በታች ፡ ተደረገች ፡ በሰው ፡ መክን
ያት ፡፡ ክርስቶስም ፡ አርነት ፡ ያወጣ ፡ ዘንድ ፡ መጣ ፡፡ የሰ
ውም ፡ ትውልድ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሲመለስ ፡ የቀረ
ች ፡ ፍጥረትም ፡ ከጥፋት ፡ መርገም ፡ አርነት ፡ ትወጣለች ፡፡
እስከዚያ ፡ ድረስ ፡ ምድራችን ፡ የጥፋት ፡ የመከራም ፡ የ
መጋደልም ፡ ስፍራ ፡ ናት ፡፡ ካደም ፡ ልጆችመ ፡ ጥቂት ፡ ናቸ
ው ፡ መድኃኒታቸውን ፡ አውቀው ፡ የተቀበሉት ፡ የደኑበት
ም ፡፡ ብዙ ፡ ናቸው ፡ በመንፈሳዊት ፡ ጨለማ ፡ በሞትም ፡ ጽ
ላ ፡ የተቀመጡ ፡፡ የሰው ፡ ወገን ፡ ሁሉ ፡ ቍጥራቸው ፡ ፲፻፡
ሚልዮን ፡ ያህላል ፡፡ ከርሳቸውም ፡ ፪፻፡ ሚልዮን ፡ ብቻ ፡ ና
ቸው ፡ በስም ፡ ክርስቲያን ፡ የተባሉ ፡፡ ፪፻፡፡ ሚልዮንም ፡ እ
ሥላሞችና ፡ አይሁድ ፡ የቀሩም ፡ ፯፻፡ ሚልዮን ፡ አረማው
ያን ፡ ናቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ የማያውቁ ፡ ለጣዖታትም ፡
የሚሰግዱ ፡፡ ለክርስቲያንም ፡ ይገባል ፡ ያለ ፡ ክርስቶስ ፡ ለ
ሚኖሩ ፡ ወንድሞቹ ፡ ያዝን ፡ ዘንድ ፡ ወንጌልም ፡ እስኪደ
ርስላቸው ፡ ይደክም ፡ ዘንድ ፡ ከሁሉም ፡ ይልቅ ፡ ክርስቶ
ስ ፡ እንደዘዘው ፡ ይጸልይ ፡ ዘንድ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡፡ ስምህ ፡
ይቀደስ ፡፡ መንግሥትህ ፡ ትምጻ ፡፡ ፈቃድህ ፡ በምድር ፡ ት
ሁን ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ በሰማይ ፡፡ አሜን ፡፡

## ክፍል ፫።

## ጂዎግራፊያ ፖሊቲቁ ።

ጂዎግራፊያ ፡ ፖሊቲቁ ፡ ታሳየናለች ፡ ምድሪቱን ፡ በብዙ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ክፍል ፡ ተከፍላ ፡ የሰው ፡ ትውልድ ፡ መኖርያ ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡ በጉባዔ ፡ ተሰማምተው ፡ ለብቻቸው ፡ ቢቀመጡ ፡ በየምድሪቸው ፡ በየወጋቸውም ፡ ለየመኳንንታቸውም ፡ ተገዝተው ፡ እርሳ ቸው ፡ ሕዝብ ፡ ናቸው ፡ ጉባኤያቸውም ፡ መንግሥት ፡ ት ባላለች ፡፡

የመንግሥት ፡ ሁሉ ፡ ስፍሪ ፡ ወሰንም ፡ ታለቅነትም ፡ መክፈልም ፡፡ የምንግሥት ፡ ሁሉ ፡ ስፍሪ ፡ በምድር ፡ ር ዝመትና ፡ ወርድ ፡ ባርዛቸው ፡ ይታወቃል ፡፡ ወሰንዋም ፡ ወ ደስ ፡ በተራሮች ፡ ባሕሮችም ፡ ፈሳሾችም ፡ ነው ፡ ወደስ ፡ በ መንግሥት ፡ ሕግ ፡ ተሰራ ፡፡ የመንግሥትም ፡ ሁሉ ፡ ታላቅነ ት ፡ በሚሎች ፡ ቍጥር ፡ ትታወቃለች ፡ በየወርዷና ፡ በየረዝ መቱ ፡፡ መክፈልዋም ፡ በየመንግሥት ፡ ሥርዓት ፡ ነው ፡፡

### የሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ብዛት ፡ ጠባዩም ፡ መማሯም ፡ ዕውቀ ቱም ፡ ብልሃቱም ፡ ማምለኩም ፡ ቋንቋውም ፡፡

መናቸይቱ ፡ ሕዝብ ፡ ቍጥርዋ ፡ በውነት ፡ ይታወቃል ፡ የ ሚወለደ፟ና ፡ የሚሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በድብደቤ ፡ ቢጻ ፉ ፡ ሹማምትም ፡ ይህችን ፡ ድብደቤ ፡ ወትሮ ፡ ቢጠብቁ ፡፡ የሰው ፡ ሕዝብም ፡ ሁሉ ፡ ጠባይዕ ፡ በታላቅ ፡ ነገር ፡ አንድ ፡ ሲሆን ፡ በታናሽ ፡ ነገር ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡ ይለያያሉ ፡፡ አ ንዷት ፡ ሕዝብ ፡ ልባም ፡ ናት ፡ የታመነችም ፡ ቁም ፡ ነገርን ም ፡ ትወደለች ፡ አትፈሪምም ፡፡ ሌላይቱ ፡ ሕዝብም ፡ ል ብ ፡ የላትም ፡ አሰትንም ፡ የምትወድ ፡ ፈሪም ፡ ናት ፡ አል ታመነችም ፡፡ አንዷት ፡ ሕዝብም ፡ ደህና ፡ ሥርዓት ፡ አላት ፡ ትጠብቀውማለች ፡ በጥቂትም ፡ በጅግም ፡ እግዚአብሔር ን ፡ ትፈሪለች ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ በረከት ፡ ተቀብላ ፡ በሃይማኖት ፡ በባለጠግነትም ፡ በትምህርትም ፡ በውቀት

ም ፡ በብልሃትም ፡ ታድጋለች ፡፡ ሌላ ፡ ሕዝብም ፡ ደህ ፡ በ
ጎ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አይገኝባትምና ፡ በጨለማ ፡ ትኖራለች ፡፡ እ
ውቀትና ፡ ብልሃት ፡ በማስተማርዮች ፡ ይማራሉ ፡፡ ማስ
ተማርዮችም ፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ አይነት ፡ አሉ ፡፡ በየመንግሥቱ
ም ፡ ደህንነት ፡ መጠን ፡ ይበዛሉ ፡ ወይስ ፡ ያንሳሉ ፡፡ የመን
ግሥት ፡ ሁሉ ፡ ተስፋ ፡ ወይስ ፡ ፍርሃት ፡ ዐሸክሮች ፡ ናቸው
ና ፡ እርሳቸው ፡ በጎን ፡ ነገርን ፡ ሁሉን ፡ በታናሽነታቸው ፡ ቢ
ማሩ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ቢወዱ ፡ በታላቅነታቸውም ፡ ለ
መንግሥታቸው ፡ ለሰውም ፡ ሁሉ ፡ ይጠቅማሉ ፡፡ ባይማ
ሩ ፡ ግን ፡ በልባቸው ፡ ክፋትና ፡ ጨለማ ፡ ኑረው ፡ ራሳቸው
ንና ፡ ባልንጀሮቻቸውን ፡ ይጐዳሉ ፡፡ የክርስቶስ ፡ ቃል ፡ ዝ
ም ፡ ብሎ ፡ አይቈጠር ፡ እንደህ ፡ ሲል ፡፡ ከሁሉ ፡ በፊት ፡
የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥትና ፡ ጽድቁን ፡ እሹ ፡
የሚቀርም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ያው ፡ ይጨመርላችኋል ፡፡

ስለ ፡ ማምለክም ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ እንደህ ፡ ይከፈላ
ሉ ፡፡ ፩፡ አንድን ፡ አምላክ ፡ የሚያመልኩ ፡፡ ፪፡ ብዙ ፡ አ
ማልክትንና ፡ ጣዖታትን ፡ የሚያመልኩ ፡፡ አንድን ፡ አም
ላክ ፡ የሚያመልኩ ፡ እሌህ ፡ ናቸው ፡፡ ፩፩፡ ክርስቲያን ፡
የልዩ ፡ ልዩ ፡ አይነት ፡፡ እርሳቸውም ፡ ሁላቸው ፡ በስም ፡ ለ
የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ የተቈጠሩ ፡ መንጋ ፡ ናቸው ፡ ሁላቸ
ው ፡ ግን ፡ የርሱ ፡ አይነተኛ ፡ ወገን ፡ አይደሉም ፡፡ የሁላቸ
ው ፡ መሠረት ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጽሩ ፡ ቃል ፡ ነው ፡ እር
ሱንም ፡ ብቻውን ፡ የሚከተል ፡ ቃሉንም ፡ በልቡ ፡ ጽሩ ፡
የሚጠብቅ ፡ የሚፈጽመውም ፡ ገንዘቡ ፡ ነው ፡ የቀሩትን ፡
ግን ፡ ክርስቶስ ፡ ለገንዘቡ ፡ አያውቃቸውም ፡፡ ፪፪፡ አይሁ
ድ ፡፡ ፫፫፡ እሥላሞች ፡፡

ብዙ ፡ አሕዛብም ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡ በቋንቋቸው ፡ ተለ
ዩ ፡፡ ዛሬ ፡ የታወቁ ፡ የምድር ፡ ቋንቋዎች ፡ ከ፫፻፡ ይበዛሉ ፡ ገ
ናም ፡ ያልታወቁ ፡ ብዙ ፡ ናቸው ፡፡ መጽሐፍ ፡ ቅዱስም ፡ አሁ
ን ፡ በ፻፷፡ ቋንቋዎች ፡ ተጽፎ ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ ይወጣል ፡፡

የሰው ፡ መክፈል ፡ ስራም ፡ መሻየጥም ፡፡

ሥርዓት ፡ ባለባት ፡ መንግሥት ፡ ሁሉ ፡ ሰዎች ፡ በልዩ ፡ ል
ዩ ፡ ማዕረግ ፡ ተከፈሉ ፡ እንደህ ፡፡ አካበሮች ፡፡ የመቅደ

ሰሦ ፡ አገልጋዮች ፡፡ ባላገሮችም ፡፡ ገባሮችም ፡፡ ወይስ ፡ እንደህ ፡፡ መኳንንት ፡፡ ወታደርም ፡፡ የመቅደስ ፡ አገልጋዮችም ፡፡ ባላገሮችም ፡፡ ገባሮችም ፡፡ ገባሮችና ፡ ሰራተኞችም ፡ ወይስ ፡ ከብትንና ፡ ፈረን ፡ ለማብዛት ፡ ደደክማሉ ፡ እንደ ፡ ገባሮች ፡ አራሾችም ፡ ተራራውንም ፡ የሚወቅሩ ፡ ሰዎች ፡ ተካዮችም ፡ ከብትንም ፡ የሚያሳድጉ ፡ ዓሣ ፡ አዕማጀችም ፡ አደኞችም ፡ የሚቀሩም ፡፡ ወይስ ፡ የተገኘውን ፡ ነገር ፡ ይሰራሉ ፡ በብረት ፡ በንጨትም ፡ በደንጊያም ፡ በሌሎች ፡ ማነራሎችም ፡ በፈትልም ፡ ሸማኖችም ፡ የሚቀሩም ፡፡ ወይስ ፡ ይነግደሉ ፡፡ ለሁሉም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ሥርዓት ፡ አለ ፡፡ የሰውም ፡ መኖርያ ፡ ወይስ ፡ ከተማ ፡ ነው ፡ ያገር ፡ ኃጀ ፡ የሚኖርባት ፡ ወይስ ፡ ታናሽ ፡ መንደር ፡ ወይስ ፡ መኻከለኛ ፡ የገቢያም ፡ አገር ፡፡

## ያገር ፡ መግዛት ፡ ልዮነት ፡፡

ለመንግሥት ፡ ሁሉ ፡ አንዲት ፡ ታላቅ ፡ ሥልጣን ፡ አለች ፡ ሕግን ፡ የምትሰጥ ፡ የምታደርገውም ፡፡ ደህች ፡ ሥልጣንም ፡ ሞናርኪቁ ፡ ናት ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ብቻ ፡ ቢገዛ ፡ ሕግንም ፡ ቢሰጥ ፡፡ አልተወሰነችም ፡ እርሱ ፡ በፈቃዱና ፡ ባውቀቱ ፡ ብቻውን ፡ ቢገዛ ፡፡ ተወሰነች ፡ ግን ፡ ከሕዝቡ ፡ ፈቃድ ፡ ጋራ ፡ ቢገዛ ፡፡ ሬጶብሊካም ፡ ናት ፡ ንጉሥ ፡ ባይኖር ፡ ሕዝብም ፡ ሁሉ ፡ ወይስ ፡ የሕዝብ ፡ ሽማግሎችና ፡ ታላቆች ፡ ባንድ ፡ ቢገዙ ፡፡

## የምድር ፡ ክፍል ፡፡

ምድር ፡ ባምስት ፡ ክፍል ፡ ተከፈለች ፡ እርሳቸውም ፡ እሌህ ፡ ናቸው ፡፡ ኤውሮጳ ፡ እስያም ፡ አፍሪካም ፡ አሜሪካም ፡ አውስትራልያም ፡፡

## ኤውሮጳ ፡፡

ስፍራ ፡፡ ወሰንም ፡፡ ታላቅነትም ፡፡ ኤውሮጳ ፡ በ፲፤ አርዝ ፡ በምዕራብ ፡ ርዝመት ፡ በ፷፯፤ አርዝም ፡ በምሥራቅ ፡ ርዝመት ፡ በ፴፮ና ፡ በ፸፪፤ አርዝም ፡ በሰሜን ፡ ወርድ ፡ በመኻከል ፡ ትኖራለች ፡፡ ታላቅነትዋም ፡ ከደሴቶችዋ ፡ ጋራ ፡ ፪፤ ሚልዮን ፡ ከ፯፻፶፤ ሺህት ፡ ፫፻፶፤ ሚላ ፡ ርዝመትና ፡ ወርድዋ ፡ ነው ፡፡ ከምድር ፡ ፊት ፡ ሁሉ ፡ ከ፲፫፤ ክፍል ፡ አንድ ፡ ክፍል ፡፡ ወሰን ፡፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ የሰሜን ፡ ውርጭ ፡ ባሕር ፡፡ ወደ ፡ ደቡብም ፡ መኻከለኛ ፡ ባሕር ፡፡ ወደ ፡ ምሥራቅም ፡ የመርሞሬ ፡ ባሕር ፡ ጥቁር ፡ ባሕርም ፡ ያሶውም ፡ ባሕር ፡፡ ወደ ፡ ምዕራብም ፡ ያትለንቲስ ፡ ዉቅያኖስ ፡፡ ተራሮች ፡፡ ፩፡፡ አልፆች ፡ በደቡብ ፡ ፈራንስና ፡ በላየኛ ፡ ኢጣልያ ፡ በመኻከል ፡ በሂልዌትያም ፡ በንምሳም ፡ ክፍል ፡፡ ከርሳቸውም ፡ ፫፤ ታላቆች ፡ ናቸው ፡ እርሳቸውም ፡ ሞንትብላንክ ፡ ሞንትሮሶም ፡ አርትላርም ፡ ሊዙሬም ፡ ፊንስትር ፡ አርሆርንም ፡፡ ፪፡፡ አጵኒኖች ፡ በኢጣልያ ፡፡ ፫፡፡ ጲርኔዎች ፡ በፈራንስና ፡ በስጳንያ ፡ በመኻከል ፡፡ ፬፡፡ ከርጳቶች ፡ በሁንጋርያ ፡ በትረንሲልዋኒያም ፡ በገሊቲያም ፡ በሲሌሲያም ፡ መኻከል ፡፡ ፭፡፡ ሀይሞስ ፡ በኤውሮጳ ፡ ባለች ፡ ቱርኪያ ፡፡ ፮፡፡ የንያላን ፡ ተራሮች ፡ በሲሌሲያ ፡፡ ፯፡፡ የፌኽትል ፡ ተራሮች ፡ በበይሬውት ፡፡ ፰፡፡ የሬን ፡ ተራሮች ፡ በፍሬንኪያ ፡፡ ፱፡፡ ጥቁር ፡ ደር ፡ በባደንና ፡ በዊርትምበርግ ፡ በመኻከል ፡፡ ፲፡፡ ብርቱ ፡ አልጵ ፡ በስዋቢያ ፡፡ ፲፩፡፡ የቲሪንገን ፡ ደር ፡ በሰክስን ፡፡ ፲፪፡፡ ሃርጽ ፡ በሰክስን ፡፡ ፲፫፡፡ የሚታሎች ፡ ተራሮች ፡ በኖርዌግን ፡፡ ፲፬፡፡ የኡራል ፡ ተራሮች ፡ በሩስያ ፡ በኤውሮጳና ፡ በስያ ፡ መኻከል ፡፡ ካፆች ፡፡ ካጵ ፡ ፊኒስተሬ ፡ በስጳንያ ፡፡ ካጵ ፡ ሰን ፡ ዊንቸንጽ ፡ በፆርቱጋል ፡፡ ካጵ ፡ ማተጳን ፡ በሞርኣ ፡፡ የሰሜንም ፡ ራስ ፡ በኖርዌግን ፡፡ ውልካኖች ፡፡ ኤትናና ፡ ዌሱውው ፡ በኢጣልያ ፡ ሀክላም ፡ ከሌሎች ፡ ጋራ ፡ በኢስለንድ ፡፡

## ባሕሮችና ፡ የባሕር ፡ ደጆች ፡፡

፩፤ የውርጭ ፡ ባሕር ፡ ከጉበቱ ፡ ከነጭ ፡ ባሕር ፡ ጋራ ፡፡ ፪፡፡

የስከንዲናዊያ ፡ ባሕር ፡ ከኖርዌግን ፡ ባሕርና ፡ ከሰሜን ፡ ባሕር ፡ ጋራ ። የሰሜን ፡ ባሕርም ፡ በከትገት ፡ በሆንድም ፡ በታናሽና ፡ በታላቅ ፡ በልትም ፡ ከምሥራቅ ፡ ባሕር ፡ ጋራ ፡ ይገጠማል ። ከምሥራቅ ፡ ባሕርም ፡ የሊፍላንድ ፡ የፊንለንድም ፡ የቦትኒያም ፡ ጉበቶች ፡ ይነሣሉ ። ፫፡ ያትለንቲስ ፡ ባሕር ፡ ወደስ ፡ የምዕራብ ፡ ወቅያኖስ ። እርሱም ፡ በእንግሊስ ፡ መስና ፡ በከለደስ ፡ ደጅም ፡ አድርጎ ፡ ከሰሜን ፡ ባሕር ፡ ጋራ ፡ ይገጠማል ። ከርሱ ፡ ዘንድም ፡ ያኲታኒያና ፡ የቢስካያ ፡ ባሕሮች ፡ አሉ ። ፬፡ መካከለኛ ፡ ባሕር ፡ በግብረልታር ፡ ደጅ ፡ ከምዕራብ ፡ ወቅያኖስ ፡ ጋራ ፡ ይገጠማል ። በኤውሮጳም ፡ በስያም ፡ በአፍሪካም ፡ በመካከል ፡ ይኖራል ። የመካከለኛ ፡ ባሕርም ፡ ክፍሎች ፡ ወደስ ፡ ጉበቶች ፡ እሌህ ፡ ናቸው ። የኤትሩርያ ፡ ባሕር ። ያድርያም ፡ ባሕር ። የዮንያ ፡ ባሕርም ። የሩምም ፡ አርኪጴላጎስ ። የደርደኔሎችም ፡ መንገድ ። የመርሞራ ፡ ባሕርም ። የቈንስታንቲኒያ ፡ ደጅም ። ጥቁር ፡ ባሕርም ። የፊዎደስያ ፡ ደጅም ። ያሶው ፡ ባሕርም ። የ ምድር ፡ ባ ሕሮች ። የለደጋና ፡ የኦኔጋ ፡ ባሕሮች ፡ በሩስያ ። የሜላርና ፡ የወተርም ፡ ባሕሮች ፡ በሽዌድን ። የጵላትን ፡ ባሕርም ፡ በሁንጋርያ ። የኪርክኒጽ ፡ ባሕርም ፡ በክሬደን ። የቦድን ፡ ባሕርና ፡ የገንፈ ፡ ባሕርም ፡ በሄልዌትያ ። ታላቅ ፡ ባሕርና ፡ የኮም ፡ ባሕርም ፡ በኢጣልያ ። ልፍሌንም ፡ ልፍኒም ፡ በኢርለንድ ። ታላቆች ፡ ወንዞች ። ዎልጋ ። ድዊናም ፡ ደንም ፡ ድነጵርም ። ዊስቱላም ። ደኑብም ። ረደንም ። ኤልብም ። ዌስርም ። ኦድርም ። ሮንም ። ጋሮናም ። ልዋርም ። ሴናም ። ጶም ። ኤብሮም ። ታጉስም ። ቴምስም ። ከሌህ ፡ በቀርም ፡ በኤውሮጳ ፡ ከ፳፬፡ የሚበዙ ፡ ወንዞች ፡ አሉ ፡ መርከቦች ፡ የሚሔዱባቸው ፡ ብዙም ፡ የተቈፈረ ፡ መስኖች ፡ አሉ ፡ በታላቅ ፡ ብሪታኒያ ፡ በፈራንስም ፡ በታችኛ ፡ ምድርም ።

ክ ሊ ማ ። ወደ ፡ ደቡብ ፡ ያለች ፡ ምድር ፡ ሙቅ ፡ ናት ፡ እርስዋም ፡ ጶርቱጋል ፡ ስጳንያም ፡ የደቡብ ፡ ፈራንስም ፡ የደቡብ ፡ ኢጣልያም ፡ የኤውሮጳ ፡ ቱርክያም ። መካከለኛ ፡ ብ

ርድና ፡ ሙቀት ፡ አለ ፡ በላዩኛ ፡ ኢጣልያና ፡ ፈራንስ ። በን
ምሳም ፡ በሄልዌትያም ፡ በሁንጋርያም ፡ በታችኛ ፡ ምድር
ም ፡ በታላቅ ፡ ብሪታንያና ፡ በኢርላንድም ፡ በደንመርክም ፡
በጵረስያም ፡ በጶሎንያም ፡ በገሊትያም ፡ በደቡብ ፡ ስከን
ደ፣ናዊያም ፡ በደቡብ ፡ ሩስያም ። ወደ ፡ ሰሜንም ፡ ያለች ፡
ምድር ፡ ብርድ ፡ ናት ።

ምድር ፡ የምታውጣ ። ካታክልት ፡ መንግሥት ። በኤ
ውሮጳ ፡ ከሚበቀሉ ፡ አታክልት ፡ ብዙ ፡ ከሌላ ፡ አገር ፡ መ
ጡ ። የሚገኝም ፡ ይህ ፡ ነው ። የብዙ ፡ አይነት ፡ እህል ፡ የ
ዛፍ ፡ ፍሬም ፡ ለምግብና ፡ ለመድኃኒት ፡ የሚሆን ። ጳታት
ስም ፡ ያታክልትም ፡ ብቋያ ፡ ቶምባሆም ፡ ከነቢስም ፡ ለሳ
ትና ፡ ለመስሪትም ፡ የሚሆን ፡ እጅግ ፡ እንጨት ፡ ወይን
ም ፡ ሩዝም ፡ ሎሚንም ፡ ቦርቱጋንም ፡ በለስም ፡ ዘይትም ፡
ለውዝም ፡ ሢካርም ፡ ጥጥም ፡ የሚቀርም ። ከንስሳም ፡
መንግሥት ። የቤት ፡ እንስሳ ፡ ሁሉ ። ያንደንድ ፡ አይነ
ትም ፡ ከምድረ ፡ በደ ፡ እንስሳ ፡ ንብም ፡ የሀር ፡ ትልም ፡
ዓሧም ፡ የሚቀርም ። ከ ሚ ነ ሪ ሎ ች ፡ መንግሥትም ።
እጅግ ፡ ብረት ፡ ነሃስም ፡ ቀርቆሮም ፡ ባዜቃም ፡ ወርቅም ፡
ብርም ፡ ልዩ ፡ ልዩም ፡ ከከበሩ ፡ ደንጎች ፡ ጭውም ፡ ባመ
ት ፡ ባመት ፡ ፴፩ ሚልዮን ፡ ቅንጣር ፡ የሚያህል ። የሚ
ነሪልም ፡ ምንጮች ።

የጅ ፡ ስራ ። መሻየጥም ። የጅ ፡ ስራ ፡ እጅግ ፡ መል
ካም ፡ በእንግልጣር ፡ በፈራንስም ፡ በታችኛ ፡ ምድርም ፡ በ
ሄልዌትያም ፡ በንምሳም ፡ ይደረጋል ። እጅግም ፡ የሚሻ
የጡ ፡ መንግሥቶች ፡ እሌህ ፡ ናቸው ። እንግልጣር ፡ ከሁ
ሉ ፡ ይልቅ ። ታችኛ ፡ ምድርም ። ፈራንስም ። ሩስያም ።
ስጳንያም ። ጶርቱጋልም ። ደንመርክም ። ሸዌድንም ። ኖ
ርዌግንም ። ጵረስያም ። ፫ የመሻየጥ ፡ ከተሞችም ። አ
ውስትርያም ። የኤውሮጳ ፡ መሻየጥ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ተ
ዘርግትዋል ። በኤውሮጳም ፡ ያለ ፡ ያልተቀረጸ ፡ ወርቅና ፡
ብር ፡ ነሃስም ፡ ፳፱ ሚልዮን ፡ ቅርሽ ፡ ያህላል ።

የኤውሮጳ ፡ ተቀማጮች ። በኤውሮጳ ፡ የሚቀመጡ ፡

ሰዎች፡ ሁሉ፡ ፪፻፡ ሚልዮን፡ ያህላሉ ። እርሳቸውም፡ ፶፡ በሚያህሉ፡ ልዩ፡ ልዩ፡ ቋንቋዎች፡ ይናገራሉ ። በማምለካ ቸውም፡ እንደዚህ፡ ናቸው ። ክርስቲያኖች፡ እርሳቸው ም፡ የሮምያ፡ ካቶሊካውያን፡ ፻፲፡ ሚልዮን ። የግሪኮች ም፡ ወይስ፡ ሩሞች፡ ፸፫፡ ሚልዮን ። ጵሮትስታንቶችም፡ ፶፡ ሚልዮን ። እሥላሞችም፡ ፫፡ ሚልዮን ። አይሁድ ም፡ ፮፡ ሚልዮን ። አረማውያንም፡ ጥቂት፡ አሉ፡ በሰ ሜን፡ ደርቻ ። በብልሃትና፡ በውቀት፡ የኤውሮጳ፡ ሰዎ ች፡ ይቀድማሉ ። በኤውሮጳ፡ ፹፩፡ ዩኒቨርሲታቶች፡ አ ሉ፡ ከብዙ፡ ሺህ፡ ከሚያንሱ፡ ማስተማርዮች፡ በቀር ። የኤውሮጳ፡ ጭፍሮች፡ በርቅ፡ ጊዜ፡ ፮፡ ሚልዮን፡ ያህላ ሉ፡ የባሕር፡ ጭፍሮችም፡ ፫፻፪። በጾር፡ ጊዜ፡ ግን፡ እጅ ግ፡ ይበዛሉ ። የሚወጣም፡ ግብር፡ ሁሉ፡ ፲፪፡ ሚልዮን፡ ቅርሽ፡ ያህላል ።

## የኤውሮጳ፡ መንግሥታት ።

፫፡ ቄሣሮች፡ አሉ፡ እርሳቸውም፡ የኣውስትርያ፡ የሩስ ያም፡ የቱርክያም፡ ቄሣሮች ። ፲፯፡ ነገሥታትም፡ እርሳቸ ውም፡ የጶርቱጋል፡ የስጳንያም፡ የፍራንስም፡ የእንግልጣ ርም፡ (ታላቅ፡ ብርታንያና፡ ኢርለንድ፡) የሆለንድም፡ የበ ልግዩምም፡ የደንማርክም፡ የሽቬድንና፡ ኖርዌግንም፡ የጵ ሩስያም፡ የናጶሊና፡ ሲቄልያም፡ የሰርዲንያም፡ የበዋርያ ም፡ የዊርትምበርግም፡ የሰክስንም፡ የሀኖወርም፡ የዮላደ ስም ። ፩፡ አርችዱክ፡ እርሱም፡ ያውስትርያ ። ፰፡ ግራንዱ ኮች፡ እርሳቸውም፡ ቶስካና፡ ባድንም፡ ሀሰንደርምስታት ም፡ ኅታም፡ መክልንቡርግም፡ ወይማርም፡ ኦልድንቡርግ ም ። ፩፡ ጋዦ፡ ኤሌክቶር፡ እርሱም፡ ሀሰን፡ ከሰል ። ፮፡ ታ ላቆች፡ ጋዦችም፡ ትረንስልዋንያና፡ ፊንለንድ ። ፩፡ መንፈ ሳዊና፡ ምድራዊ፡ ጋዢ፡ እርሱም፡ የሮምያ፡ ጳጳስ ። ከሌ ህ፡ በቀርም፡ አያሌ፡ ጋዦች፡ አሉ፡ አያሌ፡ መርክግራፎ ችም፡ አያሌ፡ ሬጱብሊኮችም፡ አያሌም፡ ለራሳቸው፡ የ ተገዙ፡ ከተሞች ።

## ፖርቱጋል ፡፡

ስፋራ ፡፡ ወሰንም ፡፡ ታላቅነትም ፡፡ የምዕራብ ፡ ርዝመት ፡ ከ፯°፡ ፱′፡ እስከ ፲፫°፡ ድረስ ፡ ነው ፡፡ የሰሜን ፡ ወርድም ፡ ከ፴፯°፡ እስከ ፵፪°፡ ድረስ ፡፡ ወደ ፡ ሰሜንና ፡ ወደ ፡ ምሥራቅም ፡ በስጳንያ ፡ ተወሰነች ፡፡ ወደ ፡ ደቡብና ፡ ወደ ፡ ምዕራብም ፡ በምዕራብ ፡ ውቅያኖስ ፡፡ ታላቅነትዋም ፡ በወርድና ፡ በርዝመት ፡ ፹፯፡፫፡ ሚላ ፡ ያህላል ፡፡

የምድር ፡ ጠባይ ፡፡ ክሊማ ፡ እጅግ ፡ ደሞቅ ፡ ነበረ ፡ ብዙ ፡ ንፋስ ፡ ባያበርደው ፡፡ ምድርም ፡ እጅግ ፡ ታፈራለች ፡ ሰው ፡ ግን ፡ አይሰራትም ፡፡ ተራሮችም ፡ ይበዙባታል ፡፡ ታላቆች ፡ ተራሮች ፡ እሌህ ፡ ናቸው ፡፡ እስትረላ ፡፡ ችንትራም ፡፡ አማራኦም ፡፡ ሞንሲክና ፡ ካልደይራኦ ፡፡ ካጽ ፡ ሰን ፡ ዊንቸንት ፡፡ ታላቆች ፡ ወንዞች ፡፡ ታኅስ ፡ ሚንኽም ፡ ዱኤሮም ፡ ጓድያናም ፡፡ በምድርም ፡ ላጎ ፡ ኦስኩራ ፡ የሚሉት ፡ ባሕር ፡ አለ ፡፡

ምድር ፡ የምታውጣ ፡ ነገር ፡፡ እጅግ ፡ ደህና ፡ ወይን ፡ ዘይትም ፡ ማርም ፡ የደቡብም ፡ ፍሬ ፡፡ ከስታንያም ፡ ጳታትስም ፡፡ ሱመክም ፡ ኮርክም ፡፡ እህልም ፡፡ እጅግ ፡ ረቂቅም ፡ የበግ ፡ ጸጕር ፡፡ ሀርም ፡፡ አባቅልቶችም ፡፡ ዓሣም ፡ የከበሩ ፡ ሚታሎችም ፡፡ ብረትም ፡፡ ነሣስም ፡፡ እጅግ ፡ ጭውም ፡፡ ደህኖችም ፡ የሚነራል ፡ ምንጮች ፡፡ የተኩሱ ፡ ሀማሞችም ፡፡

የጅ ፡ ስራ ፡፡ መሻየጥም ፡፡ የጅ ፡ ስራ ፡ ጥቂት ፡ ነው ፡ በሀር ፡ በተልባግርም ፡ በበግ ፡ ጸጕርም ፡ በቍርበትም ፡፡ የሚሰሩትም ፡ እንግዶች ፡ ናቸው ፡፡ ከነጋዶችም ፡ ብዙ ፡ እንግሊዞች ፡ ናቸው ፡፡ አያሌ ፡ መሻየጥም ፡ ወደ ፡ ሜደ ፡ ወደ ፡ ኮሎኒዮቻቸው ፡ ይሔደል ፡ በመርከብ ፡፡

ባላገሮች ፡፡ ፫፡ ሚልዮን ፡ ተኩል ፡ ያህላሉ ፡፡ በቋንቋቸውም ፡ በውቀታቸውም ፡ በልማዳቸውም ፡ ጎረቤቶቻቸውን ፡ የስጳንያን ፡ ሰዎች ፡ እጅግ ፡ ይመስላሉ ፡፡ አምልኳቸውም ፡ የሮምያ ፡ አምልኮ ፡ ነው ፡፡ ላብያተ ፡ ክርችቲያናትም ፡ ፩፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ፪፡ ሚትሮጶሊታኖችም ፡ ብዙ ፡ ቀሳ

ወስትም ፡ አሉ ፡፡ እርሳቸው ፡ ግን ፡ ሕዝብን ፡ በጨለማ ፡ ት
ተው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጽሬ ፡ ቃል ፡ ፈንታ ፡ የሰውን ፡ ት
ምርት ፡ አስተምረዋልና ፡ እግዚአብሔር ፡ በጸላቶቻቸው ፡
እጅ ፡ ሰጣቸው ፡፡

የመንግሥት ፡ መግዛት ፡፡ የንጉሥ ፡ ሥልጣን ፡ ኮርት
ስ ፡ በሚልዋቸው ፡ በመካርች ፡ ጉባኤ ፡ ተወሰነች ፡፡ ከንጉ
ሥ ፡ ልጆችም ፡ ወንድ ፡ ቢታጣ ፡ ሴት ፡ ልጁ ፡ ትነግሣለች ፡፡
ዛሬም ፡ የምትነግሥ ፡ ሴት ፡ ናት ፡ ስምዋንም ፡ ደና ፡ ማር
ያም ፡ ደግሎርያ ፡ ይሉታል ፡፡ ይህች ፡ መንግሥትም ፡ በቀድ
ም ፡ ታላቅ ፡ ነበረች ፡፡ እግዚአብሔር ፡ በህንድ ፡ በደቡብ ፡
አሜሪካም ፡ እጅግ ፡ ምድር ፡ በጃቸው ፡ ይሰጥ ፡ ነበር ፡፡ እ
ርሳቸው ፡ ግን ፡ በግፈ ፡ ገዝተዋታልና ፡ የባላገሮችንም ፡ ደህ
ንነት ፡ በማውጣት ፡ ፈንታ ፡ ቀምተዋቸዋልና ፡ ባሮችንም ፡
አድርገዋቸዋልና ፡ አሁን ፡ ብዙ ፡ አህጋር ፡ በላያቸው ፡ ተነ
ሥተው ፡ ሸፈጡ ፡ ለየራሳቸውም ፡ ተገዙ ፡፡ የእግዚአብሔ
ርም ፡ ቃል ፡ አሁን ፡ ፫፻፤ አመት ፡ የሚያህል ፡ በኤውሮጳ ፡
አብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ ላይ ፡ ሲነሣ ፡ እንግልጣርም ፡ የን
ምሳም ፡ ክፍል ፡ ሲቀበሉት ፡ ሲረቡበትም ፡ በስጳንያና ፡ በ
ጶርቱጋል ፡ በፍራንስም ፡ በኢጣልያም ፡ በሌላ ፡ አገርም ፡ አ
ልተቀበሉትም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ የተቀበሉት ፡ የ
ጵርትስታንቶችን ፡ ጉባኤ ፡ አሳደዱ ፡ እንጅ ፡፡ ዛሬም ፡ የኃ
ጢአታቸውንና ፡ የግፈቸውን ፡ ደመወዙ ፡ ይቀበላሉ ፡፡ በጶ
ርቱጋልና ፡ በስጳንያ ፡ ያሉ ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ በየጋ
ዣቸው ፡ ተቀሙ ፡፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃልም ፡ ፈንታ ፡ የጳ
ጳሳትንና ፡ የቀሳወስትን ፡ ቃል ፡ አድርገዋልና ፡ ዛሬ ፡ ሁለ
ቱን ፡ ባንድ ፡ ይጣላሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ከቀሳወ
ስታቸው ፡ ቃል ፡ ጋራ ፡፡ እግዚአብሔርም ፡ ገና ፡ ይታገሥላቸ
ዋል ፡ በእንግሊዝ ፡ እጅም ፡ የሥጋንና ፡ የነፍስን ፡ ረደት ፡
ይሰድላቸዋል ፡፡ የነፍስን ፡ ረደት ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ቃል ፡ የሚቀበሉ ፡ ጥቂት ፡ ናቸውና ፡ የሥጋ ፡ ረደት ፡ ወርቅ
ና ፡ ብር ፡ ወታደርም ፡ ብልሃትም ፡ ጸላታቸውንና ፡ ፅባቸው
ን ፡ ለማጥፈት ፡ አይጠቅማቸውም ፡፡

መክፈል :: ጶርቱጋል ፡ በሁለት ፡ ክፍል ፡ ትከፈላለች :: እርሳቸውም ፡ ያይነተኛ ፡ ጶርቱጋል ፡ መንግሥት :: የአልጋርብያም ፡ መንግሥት ::

ላይነተኛ ፡ ጶርቱጋልም ፡ ፫፤ ጵሮዊንሶት ፡ አልዋት ፡ እርሳቸውም ፡ እስትረመዷራ :: በይራም :: አንትረ ፡ ዷሮኤሚንኮም :: ትራሶስ ፡ ሞንተስም :: አሌንቴዮም ::

ታላቆች ፡ ከተሞችና ፡ አህጋርም ፡ እሌህ ፡ ናቸው ::

ሊስቦን ፡ የጶርቱጋል ፡ ሁሉ ፡ ከተማ ፡ ፵፩፤ ሺህ ፡ ቤቶችና ፡ ፴፻፻፤ ሰዎች :: ከርሳቸውም ፡ ብዙ ፡ እንግዶች ፡ እንግሊዞች ፡ ፈራንሲሶችም ፡ ንምሳዎችም ፡ አይሁድም ፡ ቫንክሎችና ፡ ሙለቶችም :: ከዚያም ፡ የሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ መቀመጫ ፡ ነው :: ፫፻ ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናት :: ፶፤ ገደሞችም :: ታላቅ ፡ ሆስጲታልም :: ቤትም ፡ ተጥለው ፡ የተገኙ ፡ ሕፃናት ፡ ወደ ፡ ሚያሳድግዋቸው :: ታላቅ ፡ ቢብልዮቴካም ፡ የንጉሥ ፡ ገንዘብ ፡ ፲፻፻፤ ትራዝን ፡ የሚዝ :: አያሌ ፡ አካዴምዮችም :: መልወጫም :: የከበረም ፡ የውኃ ፡ መንገድ ፡ በ፴፫፤ በመርሞር ፡ ቀስቶች ፡ ላይ ፡ የተሰራ :: ታላቅና ፡ ደህና ፡ መርስም ፡ ብዙ ፡ ታላቆች ፡ መርከቦች ፡ የሚጠጉበት :: ለጶርቱጋል ፡ መሻዮጥም ፡ ሊስቦን ፡ መጀመርያ ፡ ስፍራ ፡ ናት :: ቤሌምም ፡ በሚሉት ፡ በከተማ ፡ ክፍል ፡ ለሄሮኒሚቶች ፡ የተዋበ ፡ ገደም ፡ አላቸው :: ከዚያም ፡ የነገሥታት ፡ ቤትና ፡ መቃበር ፡ አሉ :: እጅግ ፡ መፈረስም ፡ ሆነ ፡ ባመት ፡ ፲፯፻፶፭፤ ምድር ፡ በተናወጠች ፡ ጊዜ ::

መፍራ :: ያውጉሥቲኖች ፡ ታላቅ ፡ ገደምና ፡ የመርሞር ፡ ቤት ፡ ክርስቲያን ፡ ወደሉበት ፡ ፮፤ የንጉሥ ፡ ቤቶችም ::

ቸንትራ ፡ የንጉሥ ፡ አምባና ፡ ገደም ፡ ወደሉበት :: ያም ፡ በ፮፤ ሚልዮንና ፡ ፫፻፤ ሺህ ፡ ቅርሽ ፡ ተሠራ ::

ቶረስ ፡ ዌድረስ :: ሴቱዋል ፡ ፲፮፻፻፤ ሰዎች ፡ የባሕርን ፡ ጨው ፡ ከዚህ ፡ እጅግ ፡ ያፈላሉ ፡ የሙስካት ፡ ወይንም ፡ ይወጣል ::

ኮይምብራ ፡ ፲፫፻፻፤ ሰዎች :: የከበረችም ፡ ኡኒዌርሲታስ ::

ጶ ር ቶ ፡ ሁለተኛ ፡ የመኖርያ ፡ ከተማ ፡ ፲፻፪፡ ሰዎች ። ደህ ና ፡ መርስም ። እጅግ ፡ የጅ ፡ ስራ ፡ እጅግ ፡ ወይንም ፡ ይወጣል ።

ብራጋ ፡ የሚትሮጶሊታን ፡ መቀመጫ ።

ብራጋንሳ ፡ የንጉሥ ፡ የመዋለጃ ፡ ስፍራ ።

ሚረንደ ፡ የወሰን ፡ ከተማ ።

ኤዎራ ፡ ፲፮፲፻፡ ሰዎች ።

ኤልወስ ፡ የወሰን ፡ አምባ ፡ በስጳንያ ፡ ደርቻ ። ፲፯፲፻፡ ሰዎች ፡ ታላቅ ፡ አርስናል ።

ሲነስ ፡ ወስኮ ፡ ደጋማ ፡ ወደ ፡ ተወለደበት ።

ያልጋርብያ ፡ መንግሥት ፡ ከተማ ፡ ተዊራ ፡ ናት ፡ ፭፲፻፡ ሰው ፡ ያለባት ።

የጶርቱጋል ፡ ግዛት ፡ በደቡብ ፡ አሜሪካ ፡ ብረሲልያ ፡ ነበረች ፡ አሁን ፡ ግን ፡ ተለየች ። በአፍሪካም ፡ ሞዛምቢክ ፡ አንጎላም ፡ ያዞሮችም ፡ ደሴቶች ፡ ማደይራና ፡ ጶርቶ ፡ ሳንቶ ፡ ናቸው ። በእስያም ፡ ጎአ ፡ ደዩም ፡ በህንድ ፡ መከዎም ፡ በጪን ፡ ከተሞች ። የቲሞር ፡ ደሴት ፡ ክፍልም ።

---

## ስጳንያ ።

ስፍራ ። ወሰንም ። ታላቅነትም ። ስጳንያ ፡ ከ፱°፡ ፲፰'፡ ከምዕራብ ፡ እስከ ፡ ፫°፡ ፲'፡ ከምሥራቅ ፡ ርዝመት ፡ ድረስ ፡ ከ፴፮°፡ እስከ ፡ ፵፫°፡ ፵'፡ ከሰሜን ፡ ወርድ ፡ ትኖራለች ። ወደ ፡ ምሥራቅና ፡ ወደ ፡ ደቡብም ፡ በመኻከለኛና ፡ በአትለንቲስ ፡ ባሕር ፡ ተወሰነች ፡ ወደ ፡ ምዕራብም ፡ በጶርቱጋልና ፡ ባትለንቲስ ፡ ባሕር ፡ ወደ ፡ ሰሜንም ፡ በቢስካያ ፡ ጉበትና ፡ በፍራንስ ። ታላቅነትዋም ፡ ፬፵፯፫፴፭፡ ሚላ ፡ ናት ።

የምድር ፡ ጠባይ ። ክሊማ ፡ በሰሜን ፡ ብርድና ፡ እርጥብ ፡ ነው ፡ በውሥጥም ፡ ትኵስና ፡ ድርቅ ። በደቡብም ፡ ትኵስና ፡ እርጥብ ። ምድርም ፡ አልተሰራችም ፡ እንጅ ፡ እጅግ ፡ ታፈራለች ። ተራሮችም ፡ ደበዛሉ ። ታላቆችም ፡ ተራሮች ፡ እሌህ ፡ ናቸው ። ጲረኔዎች ፡ የከንታብርያም ፡ ተ

ራሮች ፡ የኢቤርያም ፡ ተራሮች ፡ ሴራ ፡ ሞሬናም ። ካጳች
ም ። ካጵ ፡ ፊኒስተሬ ፡ ኦርትጋልም ፡ ተርፋልጋርም ፡ ጋታ
ም ፡ ጳሎስም ፡ ማርቲንም ። ታላቆች ፡ ወንዞችም ። ታ
ጉስ ፡ ኤብሮም ፡ ጓደልኲዊርም ፡ ሚኜም ፡ ዱአሮም ፡ ጓ
ድያናም ፡ ቲንቶም ።

ምድር ፡ የምታውጣ ። ብዙ ፡ እንስሶች ፡ ደህናም ፡
የበግ ፡ ጸጉር ፡ ፈረስም ፡ አህያም ፡ በቅሎም ፡ የሀር ፡ ትል
ም ፡ የበረኻ ፡ ብሬም ፡ ደህናም ፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ አይነትም ፡
ወይን ፡ የደቡብ ፡ ፍሬም ። ጥጥም ፡ ሡክርም ፡ ዘይትም ፡
ቶምባኾም ፡ እህልም ፡ ኮርክም ፡ ሶደም ፡ የጳፈጠ ፡ እን
ጩትም ። የከበረ ፡ ሜታሎችም ፡ ነሃስም ፡ ብረትም ፡ ባዜ
ቃም ፡ የባሬድ ፡ ጭውም ፡ የወጽ ፡ ጭውም ።

የጅ ፡ ስራ ። መሻየጥም ። ሀር ። የተልባግርም ። ሸ
ማም ። የጉኽ ፡ ልብስም ፡ ተምበኾም ። ኮርድዋንም ።
ሰምናም ። ክርታስም ። ማስተወትም ። የብረት ፡ ስራም ፡
ለጉደያቸው ፡ ግን ፡ አይበቃም ። ወደ ፡ ሌላ ፡ አገር ፡ የሚሻ
የጥ ፡ ደህ ፡ ነው ። በግ ፡ የበግ ፡ ጸጉርም ፡ ወይንም ፡ ወርቅ
ም ፡ ብርም ።

ባላገሮች ። ፲፩፡ ሚልዮን ፡ ያህላሉ ። ቋንቋቸውም ፡ የ
ጶርቱጊዝን ፡ ቋንቋ ፡ ይመስላል ፡ እንጅ ፡ ለብቻው ፡ ነው ።
አምልኳቸውም ፡ የሮምያ ፡ አምልኮ ፡ ነው ። ፷፡ ሜትሮ
ጶሊታኖችም ፡ ፶፩፡ ኤጲስቆጶሳትም ፡ አልዋቸው ። ጵሮትስ
ታንቶችም ፡ በቅድም ፡ በዚች ፡ መንግሥት ፡ እጅግ ፡ ተሳደ
ዱ ፡ ማንም ፡ ጥቂት ፡ ሲጠራጠር ፡ በቄስ ፡ ወይስ ፡ በጳጳስ ፡
በትምህርቱ ፡ ወይስ ፡ ባካሔደ ፡ በሞነክሶች ፡ ፍርድ ፡ ሞ
ተ ። አሁን ፡ ግን ፡ አለማመን ፡ በዝትዋልና ፡ ያች ፡ ፍርድ ፡
ተሻረች ። ከቅድምም ፡ ጵሮትስታንቶችን ፡ የእግዚአብሔር
ን ፡ ቃል ፡ ተከታዮች ፡ እንደ ፡ አሳደዱ ፡ እንደሁም ፡ አሁን ፡
ሞነክሶችንና ፡ ቀሳወስታቸውን ፡ ያሳደሉ ።

የመንግሥት ፡ መግዛት ። እንደ ፡ ጶርቱጋል ፡ ነው ።
የንጉሥ ፡ ፈቃድ ፡ በኮርተስ ፡ ጉባኤ ፡ ተወሰነች ። በንጉሥ ፡
ሞትም ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ባይኖር ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ትነግሣለች ።
ዛሬም ፡ የሞተው ፡ ንጉሥ ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ታናሽ ፡ ስትሆን ፡

እናትዋ ፡ ትነግሣለች ፡ ዕድሜዋ ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡፡ የልጇቱም ፡ ስም ፡ ኢሳቤላ ፡ ነው ፡፡ እናትዋም ፡ ክርስቲና ፡ ትባላለች ፡፡ የሞተ ፡ ንጉሥ ፡ ወንድም ፡ ግን ፡ ካርሎስ ፡ የሚባል ፡ መንግሥትን ፡ ይፈልጋል ፡ ስለዚህ ፡ አሁን ፡ ፲፡ አመት ፡ የሚያህል ፡ ጾርን ፡ ያደርጋሉ ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡ እንደሁም ፡ አገራቸውን ፡ ያጠፋሉ ፡፡

መክፈል ፡፡ በ፲፬፡ በቅድም ፡ መንግሥታት ፡ በነበሩ ፡ ክፍሎች ፡ ስጳንያ ፡ ትከፈላለች ፡፡

## ፩፡ አደስ ፡ ክስቲልያ ፡፡

እርስዋም ፡ በ፭፡ ግዛቶች ፡ ተከፈለች ፡፡ ፩፩፡ መድሪድ ፡፡ ፪፪፡ ቶሌደ ፡፡ ፫፫፡ ጓደለክሳ፡፡ ፬፬፡ ኵንካ ፡፡ ፭፭፡ ለመንካ፡፡

መድሪድ ፡ ታላቅ ፡ ከተማ ፡፡ ፳፲፻፡ ቤቶች ፡ ፲፯፻፻፡ ሰዎችም ፡፡ ፹፯፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናትም ፡ ፹፩፡ ገደሞችም ፡፡ የንጉሥ ፡ ቤት ፡ ታላቅና ፡ ውብ ፡ ነው ፡ የሥእል ፡ ታላቅ ፡ መሰብሰብያ ፡ አለበት ፡ የናቱራልያም ፡ መሰብሰብያ ፡ ቢብልዮቴካም ፡ የከዋክብትም ፡ መጠበቅያ ፡፡ የትምርትም ፡ አታክልት ፡፡ ፲፫፡ አካደምዮችም ፡፡ ሰን ፡ ፈርናንደ ፡ የሚሉትም ፡ ሆስጲታል ፡፡ አምፌቴያትርም ፡ ለመጫወት ፡፡ የንጉሥ ፡ አምቦች ፡ ብዋንርቲሮ ፡ እልጽራደም ፡ አራንደዌጽም ፡፡

ሳኬደን ፡ የከበሩ ፡ የጤና ፡ ምንጮች ፡ ያሉባት ፡፡

ቶሌደ ፡ በታጉስ ፡ ደር ፡ ፳፭፲፻፡ ሰዎች ፡፡ የሜትሮጶሊጣን ፡ መቀመጫ ፡ ኡኒዌርሲታስም ፡፡

ጓደለክስራ ፡ ፲፭፲፻፡ ሰዎች ፡፡ ከዚያ ፡ እጅግ ፡ ደህና ፡ ጉኽ ፡ ይሰራሉ ፡፡

አልሜደ ፡ የባዜቃ ፡ ተራራ ፡ ወደለባት ፡፡

ተለዌራ ፡ ደለረደና ፡ ታላቅ ፡ ማስተማርያ ፡፡ የሐርም ፡ መስሪያ ፡፡

## ፪፡ የቅድም ፡ ክስቲልያ ፡፡

በ፬፡ ክፍል ፡ ተከፈለች ፡፡ ፩፩፡ ቡርጎስ ፡፡ ፪፪፡ ሶርያ ፡፡ ፫፫፡ ስጎቪያ ፡ ፬፬፡ ስዊላ ፡፡

ቡርጎስ ፡ ፲፩፲፻፡ ሰው ፡፡ የሜትሮጶሊታን ፡ መቀመጫ ፡፡ ኡኒዌርሲታስ ፡፡ የበግ ፡ ጸጕርም ፡ ገቢያ ፡፡

ሰንታንድር ፡፡ ፱፻፡ ሰዎች ፡ መርስም ፡ የመሻየጥም ፡ ስፍራ ፡፡

ስጎቪያ ፡ ፱፲፻፡ ሰዎች ፡፡ የብር ፡ መቅረጫ ፡፡ የትረያኑስ ፡ ውኃ ፡ መንገድ ፡፡ የረቂቅ ፡ ጉኝ ፡ መስሪያ ፡፡ የበግ ፡ ጸጉር ፡ መሻየጥ ፡፡

ሰን ፡ ኢልድፎንሶ ፡ የንጉሥ ፡ አምባ ፡፡ የሥእልና ፡ የተጸረቡ ፡ አምሳል ፡ መሰብሰብያ ፡፡ የማስተወትም ፡ መስሪያ ፡፡

እስኩርያል ፡ የንጉሥ ፡ ታላቅ ፡ አምባ ፡ መሥሪቱ ፡ ፲፡ ሚልዮን ፡ ብር ፡ የፈጀ ፡ ፲፬፲፻፡ መሳኮት ፡ የብርሃን ፡ ማስተወት ፡ ደጆች ፡ ያሉበት ፡፡ ታላቅ ፡ ቢብልዮቴካም ፡፡ የነገሥታትም ፡ መቃበር ፡፡

፫፡ አስቱርያ ፡፡

ኦዌደ ፡ ፯፲፻ ፡ ሰዎች ፡፡ ኡኒቬርሲታስ ፡፡ የነፍጥም ፡ መስሪያ ፡፡ የስራ ፡ ቤት ፡ ለክፉ ፡ አድራጎች ፡፡ የተጣሉ ፡ ሕፃናትም ፡ ቤት ፡፡

፬፡ ገሊጽያ ፡፡

ስን ፡ ያጎ ፡ ደ ፡ ኮምጶስተላ ፡፡ ፴፰፲፻፡ ሰዎች ፡ የሚትሮጶሊታን ፡ መቀመጫ ፡ ኡኒቬርሲታስ ፡፡ ለነፍሳቸውም ፡ መድኃኒት ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ክርስቶስን ፡ የማያውቁ ፡ ወደዚህ ፡ ይሔደሉ ፡፡

ኮሩና ፡ ፲፬፲፻፡ ሰዎች ፡፡ መርስ ፡ የመርከቦችም ፡ ማበርያ ፡ ግምብ ፡፡ እጅግ ፡ መሻየጥም ፡፡ የተልባግርና ፡ የቦርኔታ ፡ መስሪያ ፡፡

ፈሮል ፡ የጾር ፡ መርስ ፡ የነፍጥና ፡ የመድፍም ፡ መሰብሰብያ ፡፡

፭፡ ሌዎን ፡፡

ወለደሊድ ፡ ፳፭፲፻፡ ሰው ፡ ኡኒቬርሲታስ ፡፡ ጌዎግራፊቂ ፡ አካደሚያ ፡፡ መስሪዮችም ፡፡

ሰለመንካ ፡ ፲፫፲፻፡ ሰው ፡፡ የስጳንያ ፡ መጀመርያ ፡ ኡኒቬርሲታስ ፡፡

ኪዊደድ ፡ ሮድሪጎ ፡ ፰፲፻፡ ሰው ፡ ብርቱ ፡ አምባ ፡፡

## ፮፡ እስትረማዱራ ።

ባዳዮጆ ፡ በጓዲያና ፡ ወንዝ ፡ ፲፪፲፻፡ ሰው ። የወሰን ፡ አምባ ።

ዖሊቨንሴ ፡ ፯፲፻፡ ሰው ።

## ፯፡ አንዳሉስያ ።

ኮርዶባ ፡ በጓዳልኩዊር ፡ ወንዝ ፡ ፫፻፻፡ ሰው ። የተዋበች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ። የፈረስ ፡ ማሳደግያና ፡ ገቢያ ። ሉካኑስና ፡ ፪፡ ሴነኮች ፡ ከዚህ ፡ ተወለዱ ።

ስዊልያ ፡ ታላቅ ፡ ከተማ ። መከበብያዋም ፡ ፻፳፯፡ ግምብ ፡ አለው ። ፲፫፲፻፡ ቤቶች ። ፱፻፻፡ ሰዎች ። የሚትሮጶሊታን ፡ መቀመጫ ። ታላቅ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ የኮሎምብ ፡ መቃበር ፡ ወደለበት ። የትምበኾ ፡ መስሪያ ። ብዙም ፡ የሀር ፡ መስሪዮች ። የባሕር ፡ መሻዬጥ ። የሮምያ ፡ ቄሣሮችም ፡ ትረያኑስ ፡ ሃድርያኑስም ፡ ቴዎደስዮስም ፡ ከዚህ ፡ ተወለዱ ።

ኼሬስ ፡ ፳፲፻፡ ሰው ፡ እጅግ ፡ ወይን ፡ ከዚህ ፡ ይወጣል ።

ካዲክስ ፡ የመሻዬጥ ፡ መጀመርያ ፡ ከተማ ፡ በስጳንያ ፡ ፲፫፯፻፡ ቤቶች ፡ ፫፲፻፡ ሰዎች ።

ጊብረልጣር ፡ እጅግ ፡ ብርቱ ፡ ከተማ ፡ የእንግሊዞች ፡ ገንዘብ ፡ በስጳንያ ። ደህና ፡ መርስ ። ፱፲፻፡ ሰው ። እድግ ፡ መሻዬጥ ።

## ፰፡ ግራነደ ።

ግራነደ ፡ ፫፲፻፡ ሰው ። በድሮ ፡ የእስላሞች ፡ ነገሥታት ፡ መቀመጫ ። የተዋበች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ። ኡኒዌርሲታስም ። የሀርም ፡ መስሪዮች ።

መለጋ ፡ ፮፻፻፡ ሰዎች ። ደህና ፡ መርስ ። እጅግ ፡ መሻዬጥ ፡ በወይን ፡ በዘይትም ፡ በደቡብ ፡ ፍሬም ፡ በሀርም ። ደህና ፡ ወይንም ፡ ከዚህ ፡ ይበቀላል ።

## ፱፡ ሙርጽያ ።

ሙርጽያ ፡ ፴፮፲፻፡ ሰው ። የሀር ፡ መስሪያ ። የጤና ፡ ምንጭም ።

ክርታግና ፡ ፷፱፻፻፡ ሰው ። አምባ ። ደህና ፡ መርስ ። ለባሕር ፡ ጾርም ፡ ያለ ፡ መድፍና ፡ ነፍጥ ፡ ከዚያ ፡ ይሰበሰባል ። መሻየጥ ።

## ፲፡ ዋለንጪ ።

ዋለንጪ ፡ ፲፻፻፡ ሰው ። ግሪ.ውም ፡ የተባለ ፡ መርስ ። የሜትሮጶሊታንም ፡ መቀመጫ ። ታላቅ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንም ። ኡኒቨርሲታስም ። የሀር ፡ መስሪያም ። መሻየጥም ።

አሊካንታ ፡ ፳፻፻፡ ሰዎች ። መርስ ። እጅግ ፡ መርከቦችና ፡ መሻየጥ ። ብዙ ፡ ወይንም ።

## ፲፩፡ ካተሎንያ ።

በርችሎና ፡ ፲፫፻፻፡ ሰው ። ብርቱ ፡ ከተማ ፡ መርስም ፡ ኡኒቨርሲታስም ፡ ታላቅ ፡ አርስናልም ። መድፎችም ፡ ከዚህ ፡ ይቀለጣሉ ። የስጳንያ ፡ ስራ ፡ ሁሉ ፡ መጀመርያ ፡ መስሪያ ፡ ከሌላ ፡ ይልቅም ፡ በሀርና ፡ በጥጥ ። እጅግ ፡ መሻየጥም ።

መታሮ ፡ ፳፩፲፻፡ ሰው ፡ የሀርና ፡ የጥጥ ፡ መስሪያ ። መሻየጥም ።

ታራጎና ፡ ፪፻፡ ሰው ፡ መሻየጥ ፡ መርስም ።

ሞንትሰረት ፡ የቤኔዲክቲኖች ፡ ገዳም ። ሎዮላም ፡ ከዚህ ፡ ተወለደ ።

## ፲፪፡ አራጎንያ ።

ሰረጎሳ ፡ በኤብሮ ፡ ወንዝ ፡ ፭፻፻፡ ሰዎች ። የሜትሮጶሊታን ፡ መቀመጫ ። ኡኒቨርሲታስም ። የሀርም ፡ የበግ ፡ ጸጕርም ፡ የሌላ ፡ ስራም ፡ መስሪዮች ። እጅግ ፡ መሻየጥም ።

## ፲፫፡ ቢስካያ ።

ጶንጶሉና ፡ ፲፩፲፻፡ ሰው ። አምባ ። ኡኒቨርሲታስም ።

ቢልባዎ ፡ ፲፭፲፻፡ ሰው ፡ የነጋዶች ፡ ቤቶች ፡ ከርሳቸውም ፡ ብዙ ፡ እንግሊዞች ። እጅግ ፡ መሻየጥ ፡ በበግ ፡ ጸጕር ።

ሰን ፡ ሴበስትያን ፡ ፲፪፲፻፡ ሰው ፡ ብርቱ ፡ መርስ ። የመብሪት ፡ ግምብ ፡ ለመርከበኞች ። እጅግ ፡ መሻየጥ ፡ በብረትና ፡ በሌላ ፡ እቃ ።

## ፲፱፡ ማዮርካ ።

የባሌኣር ፡ ደሴቶች ፡ ፩፡ ማዮርካ ፡ ከኩብሬራና ፡ ከድራኀኔራ ፡ ጋራ ፡ ፲፰፻፻፡ ሰዎች ። ፪፡ ሚኖርካ ፡ ፳፻፻፡ ሰዎች ። ከዚያም ፡ ጽርት ፡ ማሆን ፡ አለ ፡ ብርቱ ። አምባ ፡ ከላዘሬቶና ፡ ከደህና ፡ መርስ ፡ ጋራ ።

የጲትዩስ ፡ ደሴቶች ፡ ኢዊሳና ፡ ፎርመንቴራ ።

ለስጳንያም ፡ በቅድም ፡ ብዙ ፡ ግዛት ፡ ነበረ ፡ በአሜሪካ ፡ ዛሬ ፡ ግን ፡ ሁሉ ፡ ሸፈጥዋልና ፡ ጥቂት ፡ ቀረላት ።

ባፈሪካም ፡ ያለ ፡ የስጳንያ ፡ ግዛት ፡ ይህ ፡ ነው ። ቾውታ ፡ ሚሊላም ፡ ጸኖን ፡ ደዋሌጽም ፡ የከናርያ ፡ ደሴቶችም ፡ ያንቦያም ፡ የፈርናንደ ፡ ደልጾም ፡ የጋዟም ፡ ደሴቶች ።

ከእስያ ፡ ደሴቶችም ። የፌሊጲኖች ፡ የላድሮኖችም ፡ የባሽም ፡ ደሴቶች ፡ የስጳንያ ፡ ግዛት ፡ ናቸው ።

---

## ፈራንስ ።

ስፍራ ፡ ወሰንም ፡ ታላቅነትም ። ርዝመት ፡ ከ፭°፡ ምዕራብ ፡ እስከ ፰°፡ ምሥራቅ ። የሰሜን ፡ ወርድዋም ፡ ፵፪°፡ — ፶፩°፡ ነው ። ወሰንዋም ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ኢጣልያ ፡ ሄልዌትያም ፡ ንምሳም ፡ ናቸው ። ወደ ፡ ደቡብም ፡ መኻከለኛ ፡ ባሕር ። ወደ ፡ ምዕራብም ፡ ስጳንያና ፡ የምዕራብ ፡ ውቅያኖስ ። ወደ ፡ ሰሜንም ፡ የሰሜን ፡ ባሕር ፡ በልጊዩምም ፡ ንምሳም ። ታላቅነትዋም ፡ ፻፳፩፲፻፡ ሚላ ፡ በወርድና ፡ በርዝመት ፡ ታህላለች ።

የምድር ፡ ጠባይዕ ። ክሊማ ፡ መኻከለኛ ፡ ነው ። ምድርም ፡ ባያሌ ፡ ስፍራ ፡ እንጅ ፡ ፍርያም ፡ ናት ። ተራሮች ። ጲረኔዎች ። አልጶችም ። ዩራም ። አርደኖችም ። የኦወርኘም ፡ ተራሮች ። ሴወኖችም ። ወጌሶችም ። ካጶች ። ካጵ ፡ ፊኒስተሬና ፡ ካጵ ፡ ደላሆክ ። ታላቆች ፡ ወንዞች ። ልዋር ፡ ጋሮናም ፡ ደርደኝም ፡ ሴናም ፡ ሮናም ፡ ረይንም ። አያሌም ፡ የተቈፈሩ ፡ መስኖች ፡ መርከብ ፡ የሚሰርባቸው ።

ምድር ፡ የምታወጣ ። እህል ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ወይንም ፡ ዘይትም ፡ ከጽርም ፡ ለውዝም ፡ ከስታንያም ፡ የዛፍም ፡

ፈረ : አጅግ :: ማርም : ሰፈራንም : የተልባግርም : ከነቢስ ም : ሀርም : ቶምባኮም : ሰምዕም : እንጨትም : ለመጸ ረብና : ለመንደድ :: ላምም : በግም : ፍየልም : ፈረስም : በቅሎም : ዓሣም :: ነሓስም : አጅግ : ብረትም : ጥቂት : ብ ረርም : ብዙም : የደንጊያ : ቀሰል : ጨውም : የማነራል : ምንጨችም ::

የጅ : ስራ :: መሻየጥም :: የሀር : ስራ : ሸሽም : የወ ርቅና : የብር : ልብስም : በጅም : የተሰራ : የሸልም : ልብ ስ : የሀርም : ሾራብና : ማሰርያ : ጉኝም : የተልባግርና : የ ሸማም : ስራ : ሁሉ : ታጴቶችም : ቀርበትም :: ነፍጥም : የዝናድና : የብረት : እቃም : ጨንም : ቦርኔታም : ዘርፍ ም : ክርታስም : ማስተወትም : የሸልምና : የጫወታ : ስራ ም : የሚቀርም :: መሻየጥም : አጅግ : ነው ::

ባላገሮች : ፴፫ ሚልዮን : ናቸው :: መጀመርያ : ቋንቋ ቸው : ፍራንሲስ : ነው :: ያለርሱም : የንምሳውን : የብር ታኝንም : የበስክንም : የኢጣልያንም : ቋንቋች : ይናገሩ ሉ :: የብዙም : አምልኮ : የሮምያ : አምልኮ : ነው : ከዚ ያም : ጋራ : ጵሮትስታንቶች : አይሁድም : እሥላሞችም : ኢያምልኳቸው : ይቀመጣሉ :: በውቀትና : በብልሃት : ፍ ራንሲሶች : አጅግ : ያድርጋሉ : በሃይማኖት : ግን : ጥቂት : ነው : የሚያድርጉት ::

የመንግሥት : መግዛት :: ንጉሥ : ከሕዝቡ : ጉባኤ : ጋራ : ይገዛል :: ሕጉን : ሥርዓትንም : አብረው : ይቈርጣ ሉ : ንጉሥም : ለተሰራች : ሕግ : ኃይሉን : ይሰጣል :: የቀ ድም : ንጉሥ : ቻርልስ : ፲ ከሕዝቡ : ጋራ : ተጣልትዋልና : ፍራንሲሶች : ሻሩት : ባመት : ፲፰፴ :: ሌላውንም : ልዊስ : ፊሊጵ : የሚሉትን : ዘመዱን : አነገሡት : እርሱም : ዛሬ : ይነግሣል ::

መክፈል ::

ፍራንስ : በ፹፮ ዲፓርትመንቶች : በ፫፻፷፫ ዙርዮችም : በ፪፻፹፱ ከንቶኖችም : በ፴፯፱፮ ጉባኤዮችም : ተከፈ ለች ::

## የሰሜን : ዴጳርትመንቶች ::

፩ ሲና ::

ጳሪስ : በሲና : ወንዝ : የምትኖር : የመንግሥት : ሁሉ : ከተማ : የንጉሥም : መቀመጫ :: የሚትሮጶሊታንም : መቀመጫ :: ፲፻፹፩ አደባባዮች : ፫፺ ታላቆች : ቦዮችም : ፶፺ በሮችም : ከ፩ ሚልዮንም : የሚወጡ : ሰዎች :: ታላቆች : ቤቶችና : ግምቦች : እሌህ : ናቸው :: ቱልደሪስ : የንጉሥ : መኖርያ :: ሉብር : ሙሴውምና : የናቱሬልያ : የተጸረበም : የተሣለም : ሥእል : መሰብሰብያ : ወደለበት :: ጶሌርያል : የከዋክብት : መጠበቅያ : የደከሙ : ወታደርም : ማረፊያ : ወደለበት :: የሉክሰምቡርግ : ቤትም : ያካበሮች : ጉባኤ : ወደሚከማቹበት :: እመቤታችንም : የሚልዋት : ቤተ : ክርስቲያን :: ጰንቴዎንም : ተምጽልም : የሚሉት : ግዞት :: አዲስ : ድልድልም : በሀንሪ : ፬ የተሠራ : ከተጸረበ : ሥእሉ : ጋራ :: የንጉሥም : ቢብልዮቴካ : ፫፻፶ ተራዞች : የሚደዝ :: አያሌም : የውቀት : ጉባኤ : ሙሴዎች :: የሙሲካም : ቤት : ለ፻፲፰ አዋቆችና : ለ፺፻ አሽክሮች :: የትምህርትም : አታክልት : ኡኒዌርሲታስም : ከብዙ : ታላቆችና : ታናሾች : ማስተማሮዮች : ጋራ :: የጵርትስታንቶችም : የሚስዮን : ጉባኤና : ማስተማርያ :: የመጽሐፍ : ቅዲስም : ፪ ጉባኤዮች :: ፲፯ ሆስጲታሎችም :: የጎብሊንም : የታጴቶችም : የቀይ : ልብስም : የስጋደም : የማስተወትም : የሸልምና : የጫወታም : መስሪዮች :: የከበረም : የመጽሐፍ : ማኅተምዮች :: እጅግ : መሻዮጥም ::

ሰንት : ዴኒስ : የፈረንስ : ነገሥታት : መቃበር ::

፪ ሲናና : እዋሳ ::

ወርሳልይ : ፳፺፲፻ ሰው :: የንጉሥ : የሚወደው : መኖርያ :: ግምብም :: አዲስም : የታሪክ : ሥእል : መሰብሰብያ :: የነፍጥም : መስሪያ ::

፫ እዋሳ ::

ብዋ : የስጋዴና : የቆርበት : መስሪያ ::

ኮምጼኛ ፡ የንጉሥ ፡ አምባ :: የመድፈም ፡ ማስተ
ማርያ ::

፬፣ ሴናና ፡ ማርና ::

ሜሉን :: ሞክስ ፡ የኤጲስቆጶስ ፡ መቀመጫ ::

ፎንቴንብሎ :: ቦናጰርት ፡ ከዚህ ፡ ባመት ፡ ፲፰፻፲፬፣ መን
ግሥቱን ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠ ፡ በነገሥታት ፡ እጅ ::

፭፣ ኤስና ::

ላዎን :: ስዋሶንስ :: ሰንካንተን ፡ መስሪዮች ::

፮፣ ታችኛ ፡ ሴና ::

ሩዋን ፡ ፩፻፻፣ ሰዎች :: የሚትሮጶሊታን ፡ መቀመጫ :: የ
ወርቅና ፡ የብርም ፡ መቅረጫ :: መርስም :: ታላቆች ፡ መስ
ሪዮችም :: መሻየጥም ::

ዲየጰ ፡ አምባ ፡ ፳፲፻፣ ሰው ::

ሃብር ፡ ድግረስ ፡ ፭፲፻፣ ሰው :: ብርቱ ፡ መርስ ::

፯፣ ኤውር ::

ኤብረው ፡ የኤጲስቆጶስ ፡ መቀመጫ :: ሉዌ ፡ መስሪ
ዮች ::

፰፣ ክልዋደስ ::

ካእን ፡ ፫፻፻፣ ሰዎች ፡ ኡኒዌርሲታስ ፡ መስሪዮችም ::

፱፣ ለማንሽ ::

ሸርቡርግ ፡ አምባ ፡ የጾርም ፡ መርስ :: የመርከቦችም ፡
መስሪያ :: መሻየጥም ::

፲፣ ኦርና :: አላንሶን ፡ መስሪዮች :: ፲፩፣ ኤውርና ፡
ሉዋር ::

፲፪፣ ኦብ :: ፲፫፣ ላይኛ ፡ ማርና ::

፲፬፣ ማርና :: ረይምስ ፡ ፫፻፻፣ ሰዎች :: የሚትሮጶሊታ
ን ፡ መቀመጫ :: ኤጵርኔ ፡ የሻምጳኛ ፡ ወይን ፡ ወይሚበቀ
ልበት ፡ ስፍራ ::

፲፭፣ አርደን :: ፲፮፣ ሶም :: አሚንስ ፡ ፩፻፻፣ ሰዎች ::

፲፯፣ ጳድካሌስ :: ካሌስ ፡ ፯፲፻፣ ሰዎች :: ደህና ፡ መርስ ፡
በባሕር ፡ ዳጅ ::

ቡሎኝ ፡ ፲፫፲፻፣ ሰዎች :: ደህና ፡ ወደን ::

፲፰፣ ኖርድ :: ሊል ፡ ፶፭፲፻፣ ሰዎች :: ብርቱ ፡ አምባ :: ዱ

ንኪርኽን ፡ ፳፩፲፻፡ ሰዎች ። ሠርስ ። ዋለንሴን ፡ ፲፯፲፻፡ ሰ ዎች ። ከምብሬ ፡ ፲፫፲፻፡ ሰዎች ፡ የሬኔሎን ፡ አገር ። ድዌ ፡ ፲፰፲፻፡ ሰው ፡ ኡኒዌርሲታስ ።

፲፱፡ ሞሰል ፡ መጽ ፡ አሦጣ ፡ በሞሰል ፡ ወንዝ ፡ ፱፻፻፡ ሰው ።

፳፡ ማስ ። ፳፩፡ ሚውርታ ። ናንሲ ፡ ታላቅ ፡ ከተማ ። ኡኒዌርሲታስ ። የኤጲስቆጶስ ፡ መቀመጫ ። ሉንዊል ፡ ፻፻፡ ሰዎች ።

፳፪፡ ወስሽስ ። ፳፫፡ ላይኛ ፡ ሳወና ። ፳፬፡ ላይኛ ፡ ረይ ን ። ኮልመር ፡ ፲፪፲፻፡ ሰዎች ። ሙልሀውሰን ፡ ብዙ ፡ መ ስሪዮች ።

፳፭፡ ታችኛ ፡ ረይን ። ስትራስቡርግ ፡ ፭፻፻፡ ሰው ። አ ምባ ። ኡኒዌርሲታስም ። የኤጲስቆጶስም ፡ መቀመጫ ። የጵሮትስታንቶችም ፡ ኮንሲስቶርዩም ። የከበረች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ቁመትዋ ፡ ከ፪፻፭፡ ክንድ ፡ ይወጣል ። የብርና ፡ የወርቅም ፡ መቅረጫ ።

## የምዕራብና ፡ የውሥጥ ፡ ዲጳርትመንቶች ።

፳፮፡ ፌኒስትሬ ። ፳፯፡ ኖርድኮቴ ። ፳፰፡ ሞርቢሃን ።

፳፱፡ ታችኛ ፡ ልዋር ። ናንትስ ፡ ፮፯፲፻፡ ሰዎች ።

፴፡ ኢልና ፡ ዊሌን ። ሬንስ ፡ ፳፭፲፻፡ ሰዎች ፡ ኡኒዌር ሲታስ ።

፴፩፡ ማየንና ፡ ልዋር ። አንዤር ፡ ፴፱፲፻ ፡ ሰዎች ። የኤጲ ስቆጶስ ፡ መቀመጫ ። ኡኒዌርሲታስ ። ፴፪፡ ሳርታ ። ፴፫፡ ማየን ። ፴፬፡ ሁለት ፡ ሴብሮች ። ፴፭፡ ዋንዴ ። ፴፮፡ ታ ችኛ ፡ ሸራንት ። ፴፯፡ ሸራንት ። ፴፰፡ ላይኛ ፡ ዌና ። ፴፱፡ ዌና ። ጵዋቴ ፡ ፲፰፲፻፡ ሰው ። የሜትሮጶሊታን ፡ መቀመ ጫ ፡ ኡ ዌርሲታስም ።

፵፡ ኢንድር ። ፵፩፡ ኢንድርና ፡ ልዋር ። ቱርስ ፡ ፳፲፻፡ ሰዎች ። የሜትሮጶሊታን ፡ መቀመጫ ። ፵፪፡ ልዋርና ፡ ሼ ር ። ፵፫፡፡ ሼር ። ቡርዥ ፡ ፲፯፲፻፡ ሰዎች ። ኡኒዌርሲታስ ፡ የሜትሮጶሊታንም ፡ መቀመጫ ።

፵፬፡ ልዋሬት ። ኦርሊያን ፡ ፵፪፲፻፡ ሰው ። ያሁን ፡ ንጉ

ሥ ፡ የትውልደ ፡ ስፍራ ፡፡ የሚትሮጶሊታንም ፡ መቀመጫ ፡፡
፵፫ ኔብር ፡፡ ፵፬ ዮና ፡፡ ኦክሴር ፡ ፲፰፲፻ ሰው ፡፡ ወደ
ን ፡ ይወጣል ፡፡ ሳንስ ፡ የተልባግር ፡ መስሪያ ፡፡ መሻየጥም ፡
በውኃ ፡ ሰዓት ፡፡
፵፭ ሰዎናና ፡ ልዋር ፡፡ ፵፮ አሌርስ ፡፡ ፵፯ ክሬ
ውስ ፡፡

ወደ ፡ ደቡብና ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ያሉ ፡ ዴጳርትመንቶች ፡፡

፶፡፡ ዲብስ ፡፡ ብሳንሶን ፡ ፳፫፲፻ ሰው ፡፡ አምባ ፡፡ የሚት
ሮጶሊታንም ፡ መቀመጫ ፡፡ የሰዓትም ፡ ስራ ፡ ማስተማርያ ፡፡
የውቀትም ፡ አካዴሚያ ፡፡ መቅረጫ ፡፡ ኡኒቬርሲታስም ፡፡
የቡላድና ፡ የጥጥ ፡ መስሪዮችም ፡፡ ሞንትበልያርድ ፡
፩፲፻ ሰዎች ፡፡ ተራሮች ፡ ብረትን ፡ ያወጣሉ ፡፡
፶፩ ዩራ ፡፡ ተራሮች ፡ ብርን ፡ አለበስትርንም ፡ ጨውንም ፡
ያወጣሉ ፡፡
፶፪ ኮትደር ፡፡ ዲዦን ፡ ፲፰፲፻ ሰው ፡፡ አምባ ፡፡ ኡኒቬር
ሲታስ ፡፡ የወይን ፡ ስፍራ ፡፡ ሻቲልዮን ፡ የብረት ፡ መደቀሻ ፡፡
፶፫፡፡ አደን ፡፡
፶፬ ሮና ፡፡ ልዮን ፡ የፈራንስ ፡ ሁለተኛ ፡ ከተማ ፡፡ እጅግ ፡
ምስሪዮችና ፡ መሻየጥ ፡ ፪፲፫፲፻ ሰዎች ፡፡ የሚትሮጶሊታን ፡
መቀመጫ ፡፡ አካዴሚያ ፡፡ ፲፰፻፻ ትሬዝም ፡ የሚያዝ ፡ ቢ
ብልዮቴካ ፡፡ ሆስጲታልም ፡፡ መልወጫም ፡፡ መቅረጫም ፡፡
የሀርም ፡ የታጴቶችም ፡ የወርቅና ፡ የብር ፡ ልብስም ፡ የቦር
ኔታም ፡ መስሪዮች ፡፡ እድግ ፡ መሻየጥም ፡፡
፶፭ ልዋር ፡፡ ሰንቴቴና ፡ ፲፯፲፻ ሰው ፡ ብረትን ፡ ቡላድን
ም ፡ ነፍጥንም ፡ ማሰርያውንም ፡ ይሰራሉ ፡፡
፶፮፡፡ ላይኛ ፡ ልዋር ፡፡ ፶፯፡፡ ጵዊድደም ፡፡ ክሌርሞን
ት ፡ ፫፻፻ ሰዎች ፡፡ ኡኒቬርሲታስ ፡፡ የክርታስም ፡ መስሪያ ፡፡
መሻየጥ ፡፡
፶፰ ኮሬዝ ፡፡ ፶፱ ክንታል ፡፡ ኡሪልያክ ፡ ብዙ ፡ መስ
ሪዮች ፡፡
፷፡፡ አዌሮን ፡፡ ተራሮች ፡ ነሃስን ፡ ያወጣሉ ፡፡ ፷፩ ሎት ፡፡
፷፪ ሎትና ፡ ጋሮና ፡፡

፳፫፡ ደርደኛ :: ፳፬፡ ዢሮንደ :: ቦርደ : በዢሮንደ : ወንዝ :: እጅግ : መኻየጥ :: መርስ :: የሚትሮጶሊታን : መቀመጫ :: ኡኒቬርሲታስም :: መልወጫም :: ብዙ : መስሪዎችም :: የብረት : ድልድል : በወንዝ : ላይ :: ደህና : ወደንም ::

፳፭፡ ላንድስ :: ፳፮፡ ጌርስ :: ፳፯፡ ታችኛ ች : ጺረኔ ዎች :: ጶ :: ባዮና ::

፳፰፡ ላይኛ ች : ጺረኔ ዎች :: ፳፱፡ የምሥራቅ : ጺረኔ ዎች :: ጶርጺኛን ::

፴፡ ኦድ :: ፴፩፡ አሬዠ :: ፴፪፡ ላይኛ : ጋሮና :: ቱሉሳ : ፳፻፻፡ ሰዎች :: የሚትሮጶሊታን : መቀመጫ :: ኡኒቬርሲታስም : አካዴሚያም : የከዋክብትም : መጠበቅያ ::

፴፫፡ ታርን :: ፴፬፡ ታርንና : ጋሮና :: ሞንቶባን : የጵሮት ስታንቶች : አካዴሚያ ::

፴፭፡ ህሮልት :: ሞንትጶሌር : ፵፪፲፻፡ ሰው : ኡኒቬርሲታስም ::

፴፮፡ ጋርድ :: ኒምስ : ፱፻፻፡ ሰው :: አካዴሚያ :: የሾሬብና : የሀር : መስሪዎችም ::

፴፯፡ ሎዜር :: ፴፰፡ አርዴሽ :: ፴፱፡ ድሮም :: ዋላንስ : የኤጲስቆጶስ : መቀመጫ ::

፵፡ ኢዜር :: ግሬኖብል : ፳፲፻፡ ሰው :: ኡኒቬርሲታስ ::

፵፩፡ ላይኛ ች : አልጶች :: ፵፪፡ የሮና : አፎች :: መርሰልያ :: አርጊት : አገር : ፲፻፻፡ ሰዎች : እጅግ : መኻየጥ :: ኤክስ : የሚትሮጶሊታን : መቀመጫ ::

፵፫፡ ታችኛ ች : አልጶች :: ፵፬፡ ባር :: ቱሎን : ፳፪፲፻፡ ሰው :: የጶር : መርስ ::

፵፭፡ ዎክሉስ :: አዊኛን :: በሮና : ወንዝ : የኤጲስቆጶስ : መቀመጫ ::

ከሌህ : ዲጶርትመቶችም : ሌለ : የፈረንስ : ግዛት : ደህ : ነው ::

የኮርሲካ : ደሴት :: ፻፳፮፲፻፡ ሰው :: አያቾ : የቦናጶር

ት : የልደቱ : ስፍራ :: ደግሞም : አልጊርስ : ከሥላሞች : የወሰደ : ባመት : ፲፰፴ ::

በህንድም : ጶንዲሸሪ : ከሪካልም : ሸንድርናጉርም ::

ባፍሪካም : ሴኔጋል : ጎሬም : የቡርቦን : ደሴትም ::

ባሜሪካም ፡ ካየናና : አያሌ : ደሴቶች ::

---

## ታችኛ : ምድር ::

ደህች : ምድር : በቅድም : አንዲት : መንግሥት : ሁና : አሁን : ከ፲፤ አመት : በፊት : ሁለት : መንግሥታት : ሆነች :: የበልግዩም : ሰዎች : በንጉሣቸው : በሆላንድ : ንጉሥ : ዐምፀዋልና : ለራሳቸውም : ንጉሥን : አድርገዋልና ::

በልግዩም : ወደ : ደቡብ : ናት : ሆላንድም : ወደ : ሰሜን :: የሁለታቸውም : ክሊማ : መኻከለኛ : ነው :: የሆላንድ : ምድርም : እጅግ : ዝቅ : ትላለችና : ሁሉም : ውኃም : ናት : ሁሉም : ፍርያም : ናት ::

ጉበቶችና : ውኆች :: የዙይድር : ባሕር : ደላርትም : ቢስቦሽም :: ወንዞችም :: ረይን : ማስም : ሸልደም :: ብዙ : መስኖችም : አሉ : ወንዞችን : እርሶ : በርሳቸው : የሚያገናኙ ::

ምድር : የምታወጣ :: እህል : ጾታትስም : ቶምባኮም : ተልባም : ከነቢስም : ሸልገምም : የዛፍ : ፍሬም : ወይንም : አበባም : ለመሻየጥ : እንጨትም :: እጅግ : ደህና : ላምም : በግም : ፈረስም : ንብም : ዓሣም : ብረትም : እርሳስም : ነሃስም : የደንጊያ : ቀሰልም : የሸህላ : መሬትም : ገልመደም : ደኅም : ጭውም : የሚነራል : ውኃም ::

እጅግ : መስሪዮችም : አሉ :: የሚሰሯትም : ደህ : ነው :: እጅግ : ደህና : የበግ : ጸጉር : ሸማ :: ደህናም : የተልባግር : የጥጥም : ስራ : ክርታስም : የሸህላ : ስራም :: ቶምባኾም : የብረትና : የቀርበትም : ስራ : ሡከርም : አረቂም :: ወፍጮችንና : መርከቦችንም : እጅግ : ደሰራሉ :: መሻየጥም : እጅግ : ነው ::

## በልግዩም ፡፡

ባላገሮች ፡ ፫፡ ሚልዮን ፡ ያህላሉ ፡ ከርሳቸውም ፡ ብዙ ፡ የሮማ ፡ አምልኮ ፡ ወገን ፡ ናቸው ፡፡ የሌላ ፡ አምልኮ ፡ አይነትም ፡ ሁሉ ፡ አ.የሥርዓቱ ፡ ይኖራል ፡፡ መግዛት ፡፡ ንጉሥ ፡ ሌዎጶልድ ፡ የሚሉት ፡ ንምሳዊና ፡ ጵሮትስታንት ፡ ነው ፡፡ እርሱም ፡ ካገር ፡ ጉባኤ ፡ ጋራ ፡ ይገዛል ፡፡

የመንግሥት ፡ መክፈል ፡፡

፩፡ የደቡብ ፡ ብራበንት ፡፡

ብሩሰል ፡ ከተማ ፡ የንጉሥም ፡ መኖርያ ፡ ያማረ ፡ ስፍራ ፡፡ ፳፻፻፡ ሰዎች ፡፡ ብዙ ፡ ማስተማርዮችና ፡ መስሪዮች ፡፡

ሉዌን ፡ ፲፰፲፻፡ ሰዎች ፡ ኡኒቬርሲታስ ፡፡ ዋትርሎ ፡ እንግሊዞችና ፡ ጵሩሶች ፡ አብረው ፡ በፈራንሲሶች ፡ ላይ ፡ ድል ፡ ወደነሡ ፡ ቦናጳርትንም ፡ መቱ ፡፡

፪፡፡ የሊምቡርግ ፡ ክፍል ፡፡ ፫፡ አንትወርጵ ፡፡ አንትወርጵ ፡ በሽልደ ፡ ወንዝ ፡ ፯፻፻፡ ሰዎች ፡ እጅግ ፡ መሻየጥ ፡፡ ፬፡ የምሥራቅ ፡ ፈላንደርስ ፡፡ ገንት ፡ በሽልደ ፡ ወንዝ ፡ በ፳፯፡ ደሴቶች ፡ ላይ ፡ ፫፻፡ ድልድሎች ፡ የሚያገጥምዋቸው ፡፡ ፶፯፲፻፡ ሰው ፡፡ የኤጲስቆጶስ ፡ መቀመጫ ፡፡ ኡኒቬርሲታስም ፡ ብዙ ፡ መስሪዮችም ፡፡

ብሩግስ ፡ እጅግ ፡ መሻየጥ ፡፡

፭፡ የምዕራብ ፡ ፈላንደርስ ፡፡ ኦስተንድ ፡ ብርቱ ፡ መርስ ፡ ፲፩፲፻፡ ሰዎች ፡፡ እጅግ ፡ መሻየጥ ፡፡

፮፡ ሀነጋው ፡፡ ፯፡ ናሙር ፡፡ ናሙር ፡ በማስ ፡ ወንዝ ፡ ፲፭፲፻፡ ሰዎች ፡፡ የኤጲስቆጶስ ፡ መቀመጫ ፡ በዙ ፡ መስሪዮችም ፡፡

፰፡ ሌዠ ፡፡ ሌዠ ፡ በማስ ፡ ወንዝ ፡ ፹፭፲፻፡ ሰው ፡፡ የኤጲስቆጶስ ፡ መቀመጫ ፡ ኡኒቬርሲታስም ፡ ብዙ ፡ መስሪዮችም ፡፡

## ሆላንድ ፡፡

ባላገሮች ፡ ፫፡ ሚልዮን ፡ ያህላሉ ፡፡ ያገርም ፡ አምልኮ ፡ የጵሮትስታንቶች ፡ አምልኮ ፡ ነው ፡ ሌሎችንም ፡ አይከለክሉም ፡፡

## B. ከረማኒያ ::

በኮኒያና ፡ በአደና ፡ ትከፈላለች ::

ኮኒያ ፡ የቀደም ፡ ኢቆኒዩም ፡ ፲፰፲፻ ሰዎች :: አያሌ ፡ መስሪዮች :: ደህና ፡ ገቢያ :: ቄሣርያ ፡ የረም ፡ ሜትሮጶ ሊታኙ ፡ መቀመጫ :: ተርሱስ ፡ ወደስ ፡ ጠርሴስ ፡ ቅዱስ ፡ ጳውሎስ ፡ ሐዋርያ ፡ ወደ ፡ ተወለደበት :: ዛሬ ፡ ታናሽ ፡ መ ንደር ፡ ናት :: አደና ፡ ታላቅ ፡ ከተማ ::

## C. አምሳን ::

በጥቁር ፡ ባሕር ፡ የ፪ ባሮች ፡ ግዛት ፡ በሲዋስና ፡ በትራብ ዙንት ፡ የሚኖሩ ::

ሲዋስ ፡ የቀደም ፡ ጶንጦስ ፡ የባሻና ፡ የረም ፡ ሜትሮጶ ሊታን ፡ መቀመጫ ::

ቶከት ፡ መስሪዮች :: እጅግ ፡ መሻየጥ :: ፩፻፻ ሰዎች ::

ትራብዙንት ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ፡ በጥቁር ፡ ባሕር :: ፯፻፻ ሰዎች ::

## D. መራሽ ::

መራሽ ፡ የባሻ ፡ መኖርያ :: መላጥያ ፡ የረም ፡ ሜትሮ ጶሊታን ፡ መቀመጫ ::

አያሌ ፡ ደሴቶችም ፡ ወደዚህ ፡ ደገባሉ :: እርሳቸውም ፡ እሌህ ::

*a.* የገዞች ፡ ፱ ደሴቶች ፡ በስተምቡል ፡ አንጻር ::

*b.* በረም ፡ አርኪጴላጎስም ፡ እሌህ ፡ ደሴቶች ፡ የቱርኮ ች ፡ ግዛት ፡ ሁነው ፡ ደገኛሉ :: ቴኔደስ :: ሚቲሌኔም :: ኪ ዮስም ፡ ታላቅ ፡ ደሴት ፡ ፲፫፻፻ ሰዎች :: ከተማም ፡ ኪዮ ስ ፡ ትባላለች ፡ ፩፻፻ ሰዎች ፡ ያሉባት :: ደህና ፡ ገቢያ :: የ ረም ፡ ሜትሮጶሊታንም ፡ መቀመጫ :: ሳሞስ ፡ ደሴት ፡ ፵፲፻ ሰዎች :: እጅግ ፡ ወደን :: ኮስ :: ጳጥሞስ ፡ ደሴት ፡ ቅዱስ ፡ ዮሐንስ ፡ የነበረባት ፡ ራእዩን ፡ ሲጽፍ :: ሮደስ ፡ በ መኻከለኛ ፡ ባሕር :: ፩፻፻ ሰዎች :: ቆጵሮስ ፡ ፳፻፻ ሰዎ ች :: ኒኮስያ ፡ ከተማ ፡ የረም ፡ ሜትሮጶሊታንም ፡ መ ቀመጫ ::

፳፪። ቱርኮመኒያ ፡ ወይስ ፡ የቱርኮች ፡ አርሜኒያ ፡፡

አርዝሩም ፡ በኤፍራጥስ ፡ ምንጭ ፡ ታላቅ ፡ ከተማ ፡ ፲፻፻፡ ሰዎች ፡፡ የባኘ ፡ መኖርያ ፡ የአርመን ፡ ሜትሮፖሊታን ምም ፡ መቀመጫ ፡፡ ደህና ፡ ገቢያ ፡፡

በየጸት ፡ ፲፭፲፻፡ ሰዎች ፡፡ ከርስ ፡ ብርቱ ፡ አምባ ፡ ሩሶች ፡ የወሰዱት ፡ ዛሬ ፡ ፲፫፡ አመት ፡፡

፳፫። የቱርኮች ፡ ጌዎርጊያ ፡፡

ዛሬ ፡ የሩሶች ፡ ግዛት ፡ ነው ፡፡ አኸልጺክ ፡ ብርቱ ፡ ከተማ ፡፡

፳፬። ኩርዲስታን ፡፡

የኩርዶች ፡ ምድር ፡ እርሳቸውም ፡ ቀመኞች ፡ ናቸው ፡፡

፳፭። ኢራክ ፡ ዐረቢ ፡፡

የቀደም ፡ ባቢሎንና ፡ የከለደውያን ፡ ምድር ፡፡

ባግደድ ፡ ታላቅ ፡ ከተማ ፡ በጤግርስ ፡ ወንዝ ፡፡ የባሻ ፡ መኖርያ ፡፡ እጅግ ፡ መሻየጥና ፡ መስሪዮች ፡፡ ሀላ ፡ በኤፍራጥስ ፡ ወንዝ ፡፡ የባቢሎን ፡ ፍራሾች ፡ ለዚች ፡ አገር ፡ ይቀርባሉ ፡፡

መጅድ ፡ ሁሰይን ፡ የእሥላሞች ፡ መቅደስ ፡፡ ሁሰይን ፡ የሙሀመድ ፡ አማች ፡ የዓሊ ፡ ልጅ ፡ ከዚህ ፡ ተቀብርዋልና ፡፡

በሶራ ፡ በሻትኽልዐረብ ፡ ደር ፡፡ ፭፻፻፡ ሰዎች ፡፡ እጅግ ፡ መሻየጥ ፡፡

መርደን ፡ በታላቅ ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡፡ የነስቶርዮስ ፡ ወገን ፡ የኤጲስቆጶሳቸው ፡ መኖርያ ፡፡

፳፮። አልጀዚራ ፡፡

በኤፍራጥስና ፡ በጤግርስ ፡ መኻከል ፡፡ በሴጀር ፡ ተራሮችም ፡ ላይ ፡ የየዚዶች ፡ ወገን ፡ ሰይጣንን ፡ የሚያመልኩ ፡ ይቀመጣሉ ፡፡

ዲያርብክር ፡ ከተማ ፡ ፲፻፻፡ ሰዎች ፡፡ ከርሳቸውም ፡ ብዙ ፡ ክርስቲያን ፡፡ ብዙ ፡ መስሪዮችም ፡ እጅግ ፡ መሻየጥም ፡፡

ሞሱል ፡ ብርቱ ፡ ከተማ ፡ ፮፻፻፡ ሰዎች ፡፡ የነስቶርያኖ

ች : የሊቀ : ጳጳሳቸው : መኖርያ :: ብዙ : የጥጥ : መስሪ
ዮች :: እጅግ : መሻየጥ :: የወንጌልም : መለክተኞች : ከ
ዚህ : አሉ :: የኒኒዌ : ፍራሾች : ይቀርባሉ ::

## ፳፪፡፡ ሶርያ : ወይስ : ሻም ::

ደማስቆ : (ሻም : ኤልክቢራ :) ታላቅ : ያመረችም : ከተማ : ፷፻፻፡ ሰዎች : ክርሳቸውም : ፲፭፲፻፡ ክርስቲያን :: ፪፻፡፡ መስጊዶች :: ብዙ : መስሪዮች :: እጅግ : መሻየጥ ::

ሀለብ : ታላቅ : ገቢያ : ፷፻፻፡ ሰዎች :: ብዙ : መስሪዮች :: አያሌ : አብያተ : ክርስቲያናት :: ያያሌ : ኤጲስቆጶሳትም : መቀመጫ :: ለዚህችም : ከተማ : ኢተኪያ : የቀደም : አንጾኪያ : ትቀርባለች : ዛሬም : ታናሽ : መንደር : ናት :: ተራብሉስ : በባሕር : ደር :: ደህና : ገቢያ : ፲፯፲፻፡ ሰዎች ::

በደሩት : እጅግ : መሻየጥና : መስሪዮች :: የቅዱስ : ጌዎርጊስ : መቃብር : ተብሎ : የሚያሳዩት : ቅርብ : ነው :: የወንጌል : መለክተኞች : ከዚህ : አሉ :: ሳይደ : የቀደም : ሲደና :: ደህና : ገቢያ ::

በዚያም : በኩል : የሊባኖስ : ተራሮች : አሉ :: ድሩሶች : የተባሉ : ያረማውያን : ወገን : ይቀመጡባቸዋል :: ደግሞም : ማሮኒቶች : እኩሌታ : ሮማውያን :: የሮማውያን : ገደምም : አለች ::

ሱር : የቀደም : ጢርስ : በባሕር : ደር :: ዛሬ : ታናሽ : መንደር : ናት :: ያጽማጆች : መቀመጫ :: አካ : የቀደም : ጶቶልማይስ :: ብርቱ : ከተማ :: ደህና : ገቢያም ::

እሌህን : ከተሞች : እንግሊዞች : አሁን : ወሰድዋቸው : ሙሀመድ : ዓሊን : ተዋግተው ::

---

## ጶለስቲና : የተቀደሰች : ምድር : የድሮ : ከናዐን ::

ደህች : ምድር : የተቀደሰች : ምድር : ትባላለች : እግዚአብሔር : በድሮ : ዘመን : ቅድስዋት : ነበረና : መርጽዋትማ ልና : ራሱን : በኃጢአታቸው : ለጠፋ : ለሰው : ልጆች : ይገልጽ : ዘንድ : የፍቅረኑም : ፍቃድ : ለመድኃኒታችን : ይ

ሬጵምባት ፡ ዘንድ ፡፡ ከድምሳሴ ፡ ውኃ ፡ የደነች ፡ ትውል
ድ ፡ የኖህ ፡ የልጆቹ ፡ ልጆች ፡ እግዚአብሔርን ፡ ረስተው ፡ ጣ
ዖታትን ፡ ባመለኩ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ አብርሃምንና ፡
ዘሩን ፡ መረጸ ፡ ለርሳቸውም ፡ ይህችን ፡ ምድር ፡ ርስት ፡ አ
ድርጊት ፡ ሰጣቸው ፡፡ የከናዐናውያንንም ፡ አሕዛብ ፡ ስለ ፡
ኃጢአታቸው ፡ በእሥራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ አወጣ ፡፡ እግ
ዚአብሔርም ፡ ሬቶን ፡ አዋረደ ፡ ለእሥራኤል ፡ ልጆችም ፡ ን
ጉሥ ፡ ሆነላቸው ፡ እርሳቸውንም ፡ ሕዝቡንና ፡ ርስቱን ፡ አ
ደረጋቸው ፡፡ በሙሴና ፡ በነቢያቱም ፡ አፍ ፡ ተናገራቸው ፡ ሕ
ጉንም ፡ ሥርዓቱንም ፡ ሰጣቸው ፡ የምድኃኒቱንም ፡ ተስፋ ፡
አስደረገላቸው ፡ በብዙ ፡ ተአምራትና ፡ በምልክት ፡ በመሥ
ዋዕትም ፡ በምሳሌም ፡ አጸናላቸው ፡፡ የሕዝቡንም ፡ ኃጢ
አት ፡ ታገሠ ፡ እጅግ ፡ ሲፈትኑት ፡ ሲያስቈጡትም ፡ ባለማ
መናቸው ፡ ባለመታዘዛቸውም ፡ ጣዖታትንም ፡ በማምለካ
ቸው ፡፡ የኃጢአታቸው ፡ ሚዛንም ፡ በመላ ፡ ጊዜ ፡ አረማ
ውያንን ፡ አስመጣባቸው ፡ ማርከው ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ የ
ወሰድዋቸው ፡፡ ከዚያም ፡ ፸፤ አመት ፡ ከተቀመጡ ፡ በኋ
ላ ፡ እግዚአብሔር ፡ አዘነላቸው ፡ ወደ ፡ አገራቸውም ፡ መለ
ሳቸው ፡፡ ከዚያም ፡ የሩሳሌምን ፡ ሁለተኛ ፡ ጊዜ ፡ ሠሩ ፡ መ
ቅደሳቸውንም ፡ አገራቸውንም ፡፡ ከዚያ ፡ ዘመንም ፡ ጀም
ረው ፡ ከፋርስ ፡ ከመቄደንያም ፡ ከሶርያም ፡ ከምሥርም ፡
ነገሥታት ፡ በታች ፡ ሆኑ ፡ መቀባውያን ፡ እስኪነሡ ፡ ድረስ ፡፡
እርሳቸውም ፡ የንግደችን ፡ ቀምበር ፡ አፈረሱ ፡ ከልጆቻቸ
ውም ፡ ነገሥታት ፡ ሆኑላቸው ፡፡ አይሁድ ፡ ግን ፡ ለውነተኛ ፡
ንጉሣቸው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ባልተገዙ ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ አ
ሳልፎ ፡ በሮማውያን ፡ እጅ ፡ ሰጣቸው ፡፡ ሮማውያንም ፡ ሀ
ሮድስን ፡ አነገሡ ፡ በላያቸው ፡፡ አይሁድም ፡ የዚያን ፡ ጊ
ዜ ፡ በመንፈሳዊት ፡ ጨለማ ፡ ተቀመጡ ፡፡ የእግዚአብሔር
ን ፡ ሕግ ፡ ፊደሉን ፡ ሲጠብቁት ፡ ያለቀቻቸውንም ፡ ቃል ፡ ሲ
ጨምሩለት ፡ መንፈሱን ፡ ጥላው ፡ አፈረሱት ፡፡ የሕዝቡ
ም ፡ መምህራን ፡ እርሳቸውም ፡ ፈሪሳውያንና ፡ ጻፎች ፡ ለ
ራሳቸው ፡ እውራን ፡ ነበሩ ፡ ስለዚህ ፡ ለውራን ፡ መሮች ፡
ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ተሳኑ ፡ ሁለታቸው ፡ ወደ ፡ ጕድጓድ ፡ ሳይወ

ድቁ ። እግዚአብሔርንም ፡ በውነት ፡ ፈርተው ፡ ያለምን ፡ መድኃኒት ፡ ተስፋ ፡ የጠበቁ ፡ ጥቂት ፡ ነበሩ ። የዚያን ፡ ጊዜ ንም ፡ እግዚአብሔር ፡ አንድ ፡ የተወደደውን ፡ ልጁን ፡ ሰ ደደ ፡ እርሱም ፡ በቤተልሔም ፡ ከማርያም ፡ ድንግል ፡ ተወ ለደ ፡ በቀደም ፡ እንደ ፡ ተነበየ ፡ በነቢያት ። በብዙ ፡ ምሳ ሌም ፡ በብሉይ ፡ ኪዳን ፡ እንደ ፡ ተሣለ ፡ እንደ ፡ ተመሰለ ም ፡ እንዲሁም ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በትምህርቱ ፡ በተአም ራቱም ፡ በስራውም ፡ ሁሉ ፡ በሕማማቱም ፡ በሞቱም ፡ በትን ሣኤውም ፡ የመድኃኒታችንን ፡ ስራ ፡ ሰራ ። አሥራ ፡ ሁለ ቱንም ፡ ሐዋርያቱን ፡ ላከ ፡ በዓለም ፡ ሁሉ ፡ የሕማማቱንና ፡ የትንሣኤውን ፡ ወንጌል ፡ ያስተምሩ ፡ ዘንድ ። መንፈሱን ም ፡ በታላቅ ፡ ልክ ፡ ሰጣቸው ፡ በተአምራት ፡ በኃይልም ፡ በጥበብም ፡ በሃይማኖትም ፡ መላቸው ። እርሳቸውም ፡ ለ ክርስቶስ ፡ ስም ፡ መመስከራቸውን ፡ በየሩሳሌም ፡ ጀመ ሩ ። እግዚአብሔርም ፡ ምስክራቸውን ፡ ባረከ ፡ ብዙ ፡ ሺህ ንም ፡ ካይሁድ ፡ ወገን ፡ ለሃይማኖት ፡ አስገዛ ። እንዲሁም ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ እርሱዋም ፡ በውነት ፡ በየሱ ስ ፡ ክርስቶስ ፡ የሚያምኑ ፡ ጉባኤ ፡ የምትሆን ፡ በየሩሳ ሌም ፡ ጀመረች ። በጅግ ፡ መከራና ፡ በስደትም ፡ በይሁደና ፡ በ ሰማርያ ፡ በገሊላ ፡ አገርም ፡ ተዘረጋች ። ከዚያም ፡ በሐዋር ያት ፡ ሰብከት ፡ ወጣች ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ አሕዛብም ፡ ደረሰ ች ። ያይሁድ ፡ ሕዝብ ፡ ግን ፡ ባመፃቸውና ፡ በጸላትነታቸው ፡ ኑ ረው ፡ የተሰበከላቸውን ፡ መድኃኒት ፡ ንቀዋልና ፡ እግዚአብ ሔር ፡ ከፊቱ ፡ ጣላቸው ። የሮሚያ ፡ ሥራዊትም ፡ የሩሳሌ ምን ፡ አፈረሱ ፡ ከልደት ፡ ወዲህ ፡ በ፸፡ አመት ። አይሁድ ም ፡ ባሕዛብ ፡ መካከል ፡ ሁሉ ፡ ተበተኑ ። ከዚያ ፡ ዘመን ም ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ያይሁድ ፡ ምድር ፡ የል ዩ ፡ ልዩ ፡ ሕዝብ ፡ ግዛት ፡ ሆነች ። በሮምያ ፡ ቄሣሮች ፡ ዘመ ን ፡ ኤልያ ፡ ከጲቶሊና ፡ የተባለች ፡ አገር ፡ በየሩሳሌም ፡ ስ ፍራ ፡ ተሠራች ፡ አይሁድና ፡ ክርስቲያንም ፡ ተቀመጡባት ። በሀድርያኖስ ፡ ዘምን ፡ ግን ፡ በርኮኽባ ፡ የሚያሰኝ ፡ ሐሳ ዊ ፡ መሢሕ ፡ ተነሣ ። ካይሁድም ፡ ብዙ ፡ አእላፋን ፡ አስ ቶ ፡ ክርስቲያንን ፡ አሳደደ ፡ በቄሣር ፡ ላይም ፡ ተነሣ ። ቄ

ሣር ፡ ሀድርያን ፡ ግን ፡ ተዋገው ፡ መታውም ፡ ብዙ ፡ አደሁ
ድም ፡ ሞቱ ፡፡ የቀረም ፡ ለብርቱ ፡ ባርነት ፡ ተማረኩ ፡፡ በ
ቆንስታንቲኖስ ፡ ዘመንም ፡ የሩሳሌምና ፡ ግዛትዋ ፡ ከበቀ
ደም ፡ ከበረች ፡ የቄሣር ፡ እናት ፡ ሄሌና ፡ ወደ ፡ ያ ፡ በሔደ
ች ፡ ጊዜ ፡ በወንጌል ፡ የታወቀውን ፡ ስፍራ ፡ ለማየት ፡፡ እ
ርስዋም ፡ በየሩሳሌም ፡ ስትሆን ፡ የጌታውን ፡ መቃብር ፡ ያገ
ኘች ፡ የጌታውንም ፡ መስቀል ፡ ያወጣች ፡ ትባላለች ፡፡ ደ
ረ ፡ መጽሐፍ ፡ ቅዱስን ፡ ይዘው ፡ ስፍራውንም ፡ አይተው ፡
በጣም ፡ የመረመረት ፡ የዚህ ፡ ነገርን ፡ እውነት ፡ ይጠራጠ
ራሉ ፡፡ ከዚያ ፡ ዘመንም ፡ ጀምሮ ፡ ብዙ ፡ ክርስቲያን ፡ ከቅ
ርብና ፡ ከሩቅ ፡ ተነሥተው ፡ ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ ሔዱ ፡ የክር
ስቶስን ፡ መቃብር ፡ ለማየት ፡፡ በኒቅያ ፡ ሲኖደስም ፡ የየሩ
ሳሌም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ ሆነ ፡፡ አያሌ ፡ አመት
ም ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ለቅዱስ ፡ መቃብር ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡
ተሠራች ፡፡ ከዚያ ፡ ወደ ፡ ያም ፡ ቄሣር ፡ ዩልያኖስ ፡ ከሐዲ ፡ ሃ
ይማኖትን ፡ የካደ ፡ የክርሰቲያን ፡ ነገር ፡ ለመጉደት ፡ ብሎ ፡
ካይሁድ ፡ ጋራ ፡ ወደጅነት ፡ አደረገ ፡ በየሩሳሌምም ፡ አሰበ
ሰባቸው ፡ ብርንም ፡ ሰራተኞችንም ፡ ሰጣቸው ፡ የቀደሙን ፡
የሰሎሞንን ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ሮማውያን ፡ ያፈረሱትን ፡ መ
ልሰው ፡ ይሠሩት ፡ ዘንድ ፡፡ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ከለከላቸ
ው ፡፡ ሰራተኞች ፡ የቤተ ፡ መቅደስን ፡ መሠረት ፡ በማሱ ፡ ጊ
ዜ ፡ ምድር ፡ ተናውጣለችና ፡ እሳትም ፡ ከምድር ፡ ወጣ ፡
የሚያስፈራቸው ፡ ስራቸውንም ፡ አስተዋቸው ፡፡ አንድ ፡
አመትም ፡ በኋላ ፡ ዩልያኖስ ፡ በፈርስ ፡ ለይ ፡ ባደረገ ፡ ዘምቻ ፡
ሞተ ፡፡ በሞቱም ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያኑን ፡ ከጸ
ላትዋ ፡ እጅ ፡ አደነ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ክርስቲያን ፡ በቍጥር ፡ ባለ
ማዊ ፡ ሸልምም ፡ በክብርም ፡ በሥጋዊት ፡ ደህንነትም ፡ በ
በዙ ፡ ጊዜ ፡ ባይነተኛ ፡ በመንፈሳዊት ፡ ደህንነታቸው ፡ ተጐ
ዱ ፡፡ እጅግ ፡ ፀብና ፡ መለየት ፡ ተነሣች ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ቃል ፡ ከሰው ፡ ቃል ፡ ጋራ ፡ መደብለቅ ፡ ጀምረዋልና ፡ የቤተ ፡
ክርስቲያንም ፡ አለቆች ፡ ክብራቸውን ፡ እሹ ፡ ከጌታቸው ፡
ክብርና ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ደህንነት ፡ ይልቅ ፡፡ እንደሁ
ም ፡ አይነተኛ ፡ ባፍ ፡ ብቻ ፡ ያልሆነች ፡ በልብ ፡ እንጅ ፡ ያለ

ች ፡ ሃይማኖት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ጠፋች ፡ ፍቅርም ፡
በብዙ ፡ ክርስቲያን ፡ ልብ ፡ በረደ ፡፡ ጌታችን ፡ ግን ፡ ቅናተኛ ፡
ነውና ፡ ወገኖቹ ፡ ለርሱ ፡ ብቻ ፡ የሚገባውን ፡ ክብር ፡ ለራሳ
ቸው ፡ ወይስ ፡ ለሌላ ፡ ፍጥረት ፡ ቢሰጡ ፡ ይቈጣል ፡፡ እንደ
ሁም ፡ በዚህ ፡ ሆነ ፡፡ እግዚአብሔር ፡ በቍጣው ፡ ብርቱን ፡
መቅሠፍትን ፡ አስመጣ ፡ በቤቱ ፡ ላይ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ
ም ፡ አላስወገደውም ፡፡ ይህ ፡ መቅሠፍትም ፡ ሃሰተኛ ፡ ነቢ
ይ ፡ የሙሀመድ ፡ መግዛት ፡ ነው ፡፡ የሙሀመድ ፡ ወገን ፡ በ
ልደት ፡ አመት ፡ ፯፻፴፪፤ ሙሀመድ ፡ በሞተበት ፡ አመት ፡
ወደ ፡ ሶርያ ፡ ገቡ ፡፡ ክርስቲያንም ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ከለል
ባቸው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ በተመለሱ ፡ እርሳቸው ፡ በ
እሥላሞች ፡ በአቡብክርና ፡ በዑምር ፡ ኀይል ፡ ድል ፡ በነ
ሡ ፡፡ ቂርስ ፡ ግን ፡ የየሩሳሌም ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ ባመት ፡
፯፻፴፬፤ ለዑምር ፡ ብርን ፡ ሰጠ ፡ ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ እንደይገ
ባ ፡፡ እሥላሞችም ፡ ፫፤ አመት ፡ ቈይተው ፡ ተመለሱ ፡ ገቡ
ም ፡ የሰሎሞንም ፡ ሀይክል ፡ በቀደም ፡ በነበረበት ፡ ስፍራ ፡
ላሰተኛ ፡ አምልኳቸው ፡ መቅደስን ፡ ሠሩ ፡፡ ጰለስቲናንና ፡
ሶርያን ፡ ሁሉን ፡ ገዙ ፡፡ ገናም ፡ የክርስቲያን ፡ ብዛት ፡ ዓይ
ናቸውን ፡ አልከፈቱም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ አልተመ
ለሱም ፡ ልባቸው ፡ ደንድንዋልና ፡፡ ስለዚህም ፡ የእሥላሞ
ች ፡ ኀይልና ፡ ግዛት ፡ በዛ ፡ በሩምም ፡ መንግሥት ፡ በፋርስ
ም ፡ በምሥርም ፡ በአፍሪቃም ፡ በስጳኒያም ፡ በሲቄልያ
ም ፡ ተዘረጉ ፡፡ ወደ ፡ ፍረንኮችም ፡ ምድር ፡ ገቡ ፡ ደረሱ ፡
በጅዋቲ ፡ አገር ፡ ተመቱ ፡ ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ኀይላቸው ፡
በምዕራብ ፡ በጥቂት ፡ በጥቂት ፡ ጐደለች ፡፡ በሩም ፡ መን
ግሥት ፡ ግን ፡ ግዛታቸው ፡ በዛች ፡፡ ባመት ፡ ፲፻፺፬፤ አንድ ፡
ባሕታዊ ፡ ስሙን ፡ ጴጥሮስ ፡ የሚሉት ፡ ከየሩሳሌም ፡ ወደ ፡
ሮሚያ ፡ መጣ ፡ ከጳጳስ ፡ እጅም ፡ ረዴትን ፡ ለመነ ፡ በየሩ
ሳሌም ፡ ለሚቀመጡ ፡ ወዲያም ፡ ለሚሔዱ ፡ ክርስቲያን ፡
ከሥላሞች ፡ እጅ ፡ ያድናቸው ፡ ዘንድ ፡፡ ኡርባን ፡ ሁለተኛ
ም ፡ የሮሚያ ፡ ጳጳስ ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሲኖደስን ፡ ሰበሰበ ፡
የመስቀልንም ፡ ዘመቻ ፡ በሥላሞች ፡ ላይ ፡ አዘዘ ፡፡ ሰደፍ
ንም ፡ መምዘዝ ፡ የሚችል ፡ ክርስቲያን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ የሩ

ሳሌም ፡ ሊሔድ ፡ ነበረ ። ያልሔደም ፡ ብርን ፡ ሊሰጥ ፡ ነበ
ር ። የሔደውንም ፡ ሁሉን ፡ ከኃጢአቱ ፡ ሁሉ ፡ ፈታው ። የዚ
ያን ፡ ጊዜም ፡ ብዙ ፡ አእላፋት ፡ ተሰብስበው ፡ የመስቀል
ን ፡ ጦር ፡ ለመዋጋት ፡ ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ ሔደ ። ከርሳቸው
ም ፡ ብዙ ፡ ከሞቱ ፡ እጅግ ፡ ደምም ፡ ከፈሰሰ ፡ በኋላ ፡ ጎት
ፈሪድ ፡ የሚሉት ፡ ከቡልዮን ፡ አገር ፡ የሩሳሌምን ፡ ከሥላ
ሞች ፡ እጅ ፡ ወሰደ ፡ ከዚያም ፡ ነገሠ ። ባመትም ፡ ፲፩፻፹፯፤ ሣ
ህለደን ፡ የሚባል ፡ የሥላሞች ፡ ንጉሥ ፡ አገሪን ፡ ከክርስቲያ
ን ፡ እጅ ፡ ወሰደ ። ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ፍርንጆች ፡ ደግሞ ፡ አን
ድ ፡ ጊዜ ፡ ገብተው ፡ ለጥቂት ፡ ዘመን ፡ ገዝዋት ፡ እሥላሞች
ም ፡ ደግሞ ፡ አወጥዋቸው ። እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስም ፡ ጰለስቲና
ና ፡ የሩሳሌም ፡ የእሥላሞች ፡ ግዛት ፡ ናቸው ። የክርስቲያ
ን ፡ አይነትም ፡ ሁሉ ፡ አይሁድም ፡ ወትሩ ፡ ወደዚያ ፡ ይሔደ
ሉ ። አይሁድም ፡ ያለፈችን ፡ ምስጋናቸውን ፡ ያለቅሱ ፡ ዘ
ንድ ፡ የሚመጣውንም ፡ መሢሓቸውን ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ ለ
መሔደቸው ፡ መክንያትን ፡ ያደርጋሉ ። ክርስቲያንም ፡ ቢሔ
ዱ ፡ መክንያታቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ስ
ራ ፡ የሆነበትን ፡ ክርስቶስም ፡ በሥጋ ፡ የነበረበትን ፡ ነፍሳችነን
ም ፡ ያደነበትን ፡ ስፍራ ፡ ያዩ ፡ ዘንድ ። ይህም ፡ ብቻ ፡ ቢሆን ፡
እግዚአብሔርንም ፡ በመሔደቸው ፡ በመኖሪቸውም ፡ ቢያ
መሰግኑ ፡ ሌላውንም ፡ ነገር ፡ ባይሹ ፡ ደህና ፡ የሚገባም ፡ ነው ።
ደሩ ፡ ከሚሔዱ ፡ ሁሉ ፡ እንደህ ፡ አድርገው ፡ የሚሔዱ ፡
ጥቂት ፡ ናቸው ። ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ ከሚሔዱ ፡ ብዙ ፡ አ
ሉ ፡ የነፍሳቸውን ፡ ደህንነት ፡ ባገሬቸው ፡ ያላገኙዋትን ፡ ለ
መሻት ፡ የሚሔዱ ። እርሳቸውም ፡ በከንቱ ፡ ይሔደሉ ፡ ነ
ፍሳቸው ፡ ባትለወጥ ። ዓለምን ፡ ሁሉን ፡ የሚመላውን ፡
እግዚአብሔርን ፡ በቤቱ ፡ ያላገኘው ፡ በዓለም ፡ ሁሉ ፡ አያ
ገኘውምና ። እግዚአብሔርንም ፡ ያገኘ ፡ ሁሉ ፡ በየሩሮሌ
ም ፡ ተሰቅሎ ፡ የሞተውንም ፡ የተነሣውንም ፡ ክርስቶስን ፡
አገኘ ፡ ይህም ፡ ከየሩሳሌም ፡ ከዓለምም ፡ ሁሉ ፡ ይሻላ
ል ። ያለርሱም ፡ ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ መሔድ ፡ ያለ ፡ ሃይማ
ኖት ፡ እንደ ፡ ተሰራ ፡ ስራ ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአት ፡ ነው ። እንደሁ
ም ፡ የሔደ ፡ ሲመለስ ፡ ከበፊት ፡ ካልሔደ ፡ ይከፋል ።

በጳለስቲናም : የከበሩ : ቦታች : እሌህ : ናቸው ::

የሩሳሌም : ከተማ : ስምዋ : በዐረብ : ቋንቋ : ቁድስ : ይባላል :: ባያሌ : ኮረፍቶች : ላይ : ተሠራች :: ፭፲፻፥ ሰዎች :: ከርሳቸውም : ፫፲፻፥ ወይስ : ፯፲፻፥ አይሁድ : ፯፲፻፥ ክርስቲያንም : የቀረም : እሥላሞች : ናቸው :: በጽዮን : ተራራ : ላይ : ተሠርቶ : የዳዊት : አምባ : የሚባል : የፈረንጆች : ስራ : ሁኖ : ይመስላል :: የቅዱስ : መቃበርም : ቤተ : ክርስቲያን :: የመቃበርና : የመስቀል : ስፍራ : ግን : የተሳሳተ : ይመስላል : አይነተኛ : ስፍራቸውም : አልታወቀም :: ክርስቶስ : ከከተማ : በሜደ : ተሰቅሎ : ሙትዋልና : የመቃበር : ቤተ : ክርስቲያን : ስፍራ : ግን : የዚያን : ጊዜም : በውሥጥ : ነበር :: በዚያች : ቤተ : ክርስቲያንም : የሩሞች : የፈረንጆችም : የአርመናችም : የግብጾችም : የሀበሻ : ሰዎችም : ገደሞች : በያጠገብዋ : አሉ :: ብዙ : ሌሎችም : ገደሞች : በከተማ : አሉ :: አያሌም : ከወንጌል : መለክተኞች : አሉ :: ዛሬም : አንዲት : ቤተ : ክርስቲያን : ለጵሮትስታንቶች : ተሠራለች :: ሀራም : ሸሪፍ : በዕምር : የተሠራች : የሥላሞች : የከበረች : መስጊድ : የሰሎሞን : ሀይከል : በነበረ : ስፍራ : በሞሪያ : ኮረፍታ : ላይ :: የሂናም : ቈላ : የኪድሮንም : ወንዝ : የዮሳፍጥም : ቈላ : የሰሊሆምም : መጠመቅያ : ጌትሴማኔም : ደብረ : ዘይትም : የነገሥታትና : የመሳፍንትም : መቃበሮች : የአቢሰሎም : ሃወልትም : በከተማ : ዙርያ : ደገኛሉ :: በደብረ : ዘይትም : በምሥራቅ : አጠገቡ : ቢታኒያ : አለች : ጌታችን : አልዓዛርን : ወደስነሣው :: ያንድ : ቀን : መንገድም : ከየሩሳሌም : ወደ : ምሥራቅ : የሪኮና : የሎጥ : ባሕር : አሉ ::

ቤተልሔም : የዳዊት : አገር : ጌታችን : ወደ : ተወለደበት : በኮረፍታ : ላይ : ነው :: ከዚያ : ፪፥ ታላቆች : ገደሞች : አሉ :: ሰሎሞንም : ወይስ : ኅዝቅያስ : የሰራቸው : ፫፥ መጠመቅዮች : አሉ : ውኃቸውን : ባገደ : ወደ : ቤተ : ልሔምና : ወደ : የሩሳሌም : የሚሰደ :: ኬብሮን : ፪፻፻፥ ሰዎች : የወይን : ስፍራ ::

የሪኮ : ዛሬ : ታናሽ : መንደር : ናት : አንድ : አሮጌ : የፈ

ረሰም : አምጣ : ወደላ :: የኤልሳ : ምንጭ : ቅርብ : ነው ::
የሰቲምም : ሚደ : ይቀርባል : ሰደምና : ገሞራ : በቀድሞ :
በእግዚአብሔር : ፍርድ : ስለ : ኃጢአታቸው : ወደ : ጠፉ ::
ዛሬም : ታላቅ : ባሕር : ከዚያ : ይቆማል : ውኃውም : መ
ራራና : ጭው : ነው : ይከብደልም :: የዮርደኖስ : ወንዝም :
ወደዚህ : ባሕር : ገብቶ : ይቆማል ::

ያፋ : በመኻከለኛ : ባሕር : ደር :: መርስ :: ደህና : ገቢያ ::

ልድ : ጴጥሮስ : ኤኔያስን : ወደ : ፈወሰ ::

ረምላ : ፮፤ ገደሞች :: ጋዛ : ከያፋ : ወደ : ደቡብ :: የወደ
ሬ : ዲር : ከዚያ : አለ ::

ናብሉስ : የድሮ : ሲኬምና : ሲካር : በቍላ : በዔባልና :
በገሪጺም : ተራሮች : መኻከል : ደህና : ስፍራ :: አያሌ : ሰ
ምራውያን : ከዚህ : ይገኛሉ :: ሴበስቴ : የቀድሞ : ሰ
ማርያ ::

የእስድሬሎም : ሚደ :: ታላቅና : ፍርያም : ናት :: የኪ
ሶን : ወንዝ : በከርመል : እግር : በምዕራብ : ወገንዋ : ያል
ፍባታል : ከርመልንም : ዞሮ : ወደ : መኻከለኛ : ባሕር : ይ
ገባል :: በዚች : ሚደም : በቀደም : ይዝረዔል : ዓይንደር
ም : ናይንም : ነበሩ :: የታቦር : ተራራም : በሰሜን : አጠገ
ብዋ : ነው ::

ናዝሬት : ጌታችን : ባሸክርነቱ : ወደ : ተቀመጠ : ደህና :
አግር : በተራራ : ላይ :: ያመረች : ቤተ : ክርስቲያን ::

የዮርደኖስ : ወንዝ : ምንጩ : በሆር : ተራራ : ላይ : ነ
ው : እርሱም : ደግሞ : አንቲሊበኖስ : በሚባል :: ከምን
ጩ : ጥቂት : ወርዶ : በታናሹ : በሜሮም : ባሕር : መኻከል :
ያልፋል :: ከዚያም : በኋላ : ወደ : ቍላ : ሲገባ : በጌኔዛሬ
ጥ : ወይስ : ጥብርያደስ : ባሕር : መኻከል : ያልፋል :: ከዚ
ያም : ሲወጣ : በቀና : መንገድ : ወደ : ደቡብ : ይሔደል :
ወደ : ሎጥ : ባሕር : ገብቶ : እስቲያልቅ : ድረስ ::

የጌኔዛሬጥ : ባሕር :: እርሱም : በመጽሐፍ : ቅዱስ :
የኪነረት : የጥብርያደስም : የገሊላም : ባሕር : ተባለ :: ር
ዝመቱ : ፲፤ ሚላ : ወርዱም : ፳፤ ሚላ : ያህላል :: ከዚያ
ም : በቀደም : ጥብርያደስ : ቅፍርናሆምም : ቤተሰይደም :

ሀሣዲላም ፡ የ፲፡ ከተሞች ፡ አገርም ፡ በዙሪያው ፡ ነበረ ፡፡ የክርስቶስ ፡ ነገርም ፡ ስራውም ፡ ታአምራቱም ፡ እጅግ ፡ በዚህ ፡ በኵል ፡ ሆነ ፡፡ ዛሬ ፡ ሁሉ ፡ ባድ ፡ ነው ፡ ጠበሪያ ፡ ብቻ ፡ በጥብርያድስ ፡ ስፍራ ፡ ትገኛለች ፡፡ እርስዋም ፡ ታናሽ ፡ አገር ፡ ናት ፡ በመከበብያ ፡ የተከበበች ፡ ፬፲፱፡ ወይስ ፫፲፱፡ ሰዎችም ፡ አሉባት ፡ ከርሳቸውም ፡ ብዙ ፡ አይሁድ ፡፡ ላይሁድም ፡ ታላቅና ፡ የከበረ ፡ ማስተማርያ ፡ ከዚህ ፡ አላቸው ፡፡ ደግሞም ፡ በቅፍርናሆም ፡ ስፍራ ፡ ዛሬ ፡ ታናሽ ፡ መንደር ፡ ይገኛል ፡፡ ሳፈት ፡ በተራራ ፡ ላይ ፡፡ ከዚያም ፡ አያሌ ፡ አይሁድ ፡ አሉ ፡፡ ቃና ፡ በገሊላ ፡ ታናሽ ፡ መንደር ፡፡ የረም ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡፡

ሽወመር ፡ ታላቅ ፡ መንደር ፡ ብዙ ፡ አታክልት ፡ ወደሉ ፡፡

ኻይፋ ፡ በከርመል ፡ እግር ፡ በባሕር ፡ ደር ፡፡ በከርመል ፡ ተራራ ፡ ላይም ፡ ታላቅና ፡ ያመረች ፡ ገዳም ፡ አለች ፡ ወትሩ ፡ ፮፡ ወይስ ፯፡ የከርመሊቶች ፡ ሞነክሶች ፡ ወደሉባት ፡፡

ከከርመልም ፡ አያሌ ፡ ሚላ ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ በባሕር ፡ ደር ፡ የቂሣርያ ፡ ፍራሾች ፡ አሉ ፡፡

---

የእስያ ፡ ጌዎግራፊያ ፡ መጨረሻ ፡፡

# አፍሪቃ ፡፡

አፍሪቃ ፡ ታላቅ ፡ ጴኒንሱላ ፡ ናት ፡ ገና ፡ ጥቂት ፡ የታወቀች ፡፡

ስ ፡፡ ወ ፡፡ ታት ፡፡ ርት ፡ ከምዕብ ፡ ርት ፡ ፴፯°፤ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምቅ ፡ ርት ፡ ፴፭°፤ ድረስ ፡፡ ወድ ፡ ከ፲፯°፤ ከሰ ፡ ወድ ፡ እስከ ፡ ፶፩°፤ ከደ ፡ ወድ ፡ ድረስ ፡፡ ታት ፡ ፲፩፤ ሚልዮን ፡ ሚላ ፡ ታህላለች ፡፡

የምድር ፡ ጠባይ ፡፡ ክሊማ ፡ ትኩስ ፡ ነው ፡ ባያሌ ፡ ተራሮችም ፡ ላይ ፡ ብቻ ፡ ይበርደል ፡፡ ያፍሪቃ ፡ ታላቅ ፡ እኩሌታ ፡ በሁለት ፡ በምላሽ ፡ ዙርዮች ፡ መኻከል ፡ ትኖራለች ፡ አስተካካይም ፡ በመኻከልዋ ፡ ያልፈል ፡፡ ተራሮች ፡፡ በሰ ፡ የታላቅና ፡ የታናሽ ፡ አትለስ ፡ ተራሮች ፡ በመሥእም ፡ የአበሻ ፡ ተራሮች ፡ ወደ ፡ መኻከለኛ ፡ አፍሪቃም ፡ የሚገቡ ፡ የጨረቃ ፡ ተራሮች ፡፡ በደ ፡ የሉጰታ ፡ ተራሮች ፡ በምዕብ ፡ የኮንግ ፡ ተራሮች ፡፡ ካጾች ፡፡ ጓርድፋይ ፡ ኮረንቴስም ፡ ደልጋደም ፡ በምቅ ፡፡ የበጎ ፡ ተስፋም ፡ የስሕተትም ፡ የመርፌም ፡ ካጾች ፡ በደ ፡፡ የነጭ ፡ የሀረንጓደም ፡ የሴራ ፡ ሌዎናም ፡ የሎጰጵም ፡ የጎንሳልቦም ፡ የጰልማስም ፡ ካጾች ፡ በምዕብ ፡፡ የቦና ፡ ካጵም ፡ በሰ ፡፡ ጉበቶች ፡፡ ጉበት ፡ እልኽራብ ፡ በተጉሪ ፡ የበርብራ ፡ ጉበትም ፡ የደለጎዋ ፡ ጉበትም ፡ በምቅ ፡ የታፍል ፡ ጉበትም ፡ በደ ፡ የጊኔያ ፡ ጉበትም ፡ በምዕብ ፡ የሲርቶች ፡ ጉበትም ፡ በሰ ፡፡ የባሕር ፡ ደጆች ፡፡ የግብረልታር ፡ የመንደብም ፡ የሞዘምቢክም ፡ ደጆች ፡፡ ወንዞች ፡፡ አባይና ፡ ነጭ ፡ ወንዝ ፡ በሰናር ፡ በኩል ፡ ተገናኝተው ፡ አንድ ፡ ወንዝ ፡ የሚሆኑ ፡ ኒል ፡ ተብሎ ፡፡ ቻደና ፡ ቍራ ፡ ላንድ ፡ ወንዝ ፡ ተገናኝተው ፡ ኒገር ፡ የሚሆኑ ፡፡ ሴኔጋልም ፡ ገምቢያም ፡ ዛደርም ፡ የኦረንጅ ፡ ወንዝም ፡ ዛምቤስም ፡፡ የምድርም ፡ ታላቆች ፡ ባሕሮች ፡፡ ጫድ ፡ በቡርኑ ፡ ጻናም ፡ በድምብያ ፡ ማሬዎቲስም ፡ በምሥር ፡ ሌሎችም ፡፡ በዚች ፡ ምድርም ፡ ውኃ ፡ የሌላቸው ፡ ታላቆች ፡ ያሸዋ ፡ በረኾች ፡ ይበዛሉ ፡፡

ምድር ፡ የምታወጣ ፡፡ ውኃ ፡ ወደለበት ፡ ስፍራ ፡ ሁ

ሉ ፡ እጅግ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ እህል ፡ የዛፍም ፡ ያትክልትም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ አይነት ፡ በጎ ፡ ወይንም ፡ ተምርም ፡ በለስም ፡ ኢንዲጎም ፡ ብርብሬም ፡ ቶምበኮም ፡ ጥጥም ፡ ቡንም ፡ ሡክርም ፡ ተልባም ፡ ክነቢስም ፡ ሲነመኪም ፡ ሙጫም ፡ እጣንም ፡ ከርቤም ፡ የዞጿና ፡ የሰንድ ፡ እንጨትም ፡፡ ያራዊት ፡ አይነትም ፡ ሁሉ ፡ የከብትም ፡ የአዕዋፍም ፡ ብዙ ፡ የተለያየ ፡ አይነት ፡ የሚኒራሎችም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ አይነት ፡፡

የጁ ፡ ስራ ፡ ጥቂት ፡ ነው ፡፡ የብዙ ፡ ያፍሪካ ፡ መከራና ፡ ክፉት ፡ መክንያት ፡ ሀኬት ፡ ናት ፡፡ ስለዚህም ፡ መሻየጣቸው ፡ ክፉ ፡ ነው ፡ ጥቂትም ፡ ያስቸግራልም ፡፡ መሻየጥም ፡ ሁሉ ፡ ካገር ፡ ወደገር ፡ በምትሔድ ፡ ቅፍለት ፡ ይደረጋል ፡፡

ባላገሮች ፡፡ ቍጥራቸው ፡ ተረግጦ ፡ አልታወቀም ፡ ደሩ ፡ ፻፶ ሚልዮን ፡ ያህል ፡ ይሆናሉ ፡፡ እርሳቸውም ፡ የብዙ ፡ አይነት ፡ ናቸው ፡፡ አምልኳቸውም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ነው ፡፡ በዚች ፡ ምድርም ፡ ላይ ፡ ያለች ፡ መንፈሳዊት ፡ ጨለማ ፡ ታላቅ ፡ ናት ፡፡ የእግዚአብሔርም ፡ እውቀት ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ አለች ፡፡ የሰው ፡ ብዛትም ፡ ካራዊት ፡ በታች ፡ ተዋረደ ፡፡ እግዚአብሔርም ፡ ባባታቸው ፡ በካም ፡ ኃጢአት ፡ በኃጢአታቸውም ፡ መክንያት ፡ የሰውን ፡ ልጅነት ፡ ነሥቶባቸው ፡ ለባርነት ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፡፡ ደሩ ፡ ክርስቶስ ፡ በፍቅሩ ፡ ስለርሳቸውም ፡ ሙትዋልና ፡ ለወገኖቹ ፡ ይገባል ፡ የወንጌልን ፡ ብርሃን ፡ በመካከላቸው ፡ ያበሩ ፡ ዘንድ ፡፡ ወንጌልንም ፡ ቢቀበሉ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስም ፡ በውነት ፡ ቢያምኑ ፡ እርሱ ፡ በውነት ፡ አርነት ፡ ያወጣቸዋል ፡ ወደ ፡ ሰው ፡ ልጅነትም ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልጅነት ፡ እንጂ ፡ ያደርሳቸዋል ፡፡ ይህም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ነው ፡፡ እርሱ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እንዲድን ፡ ሁሉም ፡ ወደ ፡ እውነቱ ፡ እውቀት ፡ እንዲደርሱ ፡ ይሻልና ፡፡ ለአብርሃምም ፡ የምድር ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ በዘሩ ፡ እንዲባረኩ ፡ ተስፋ ፡ አስደረገለት ፡፡ ይችም ፡ ተስፋ ፡ ትፈጸም ፡ ዘንድ ፡ በጥቂት ፡ ጀመረች ፡፡ ባያሌ ፡ ስፍራ ፡ የወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ ተልከው ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ ወሬ ፡ አስታወቁ ፡ ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ተምረው ፡ አመኑበት ፡ በሃይማኖትም ፡ ወ

ደ ፡ ሥጋና ፡ ወደ ፡ ነፍስ ፡ ደህንነት ፡ ደረሱ ፡፡ እግዚአብሔር
ም ፡ የእንግሊዞችን ፡ ልብ ፡ በፍቅር ፡ በሞላ ፡ ጊዜ ፡ በግርነት ፡
ለተቀመጡ ፡ ወንድሞቻቸው ፡ ላፍሪቃ ፡ ልጆች ፡ ያዝኑ ፡ ዘ
ንድ ፡ በግዛታቸው ፡ የተቀመጡትን ፡ ባሮች ፡ ሁሉን ፡ ፈቱ ፡
ከባሮች ፡ መርከቦችም ፡ የተገኙትን ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ሲራ ፡
ሌዎና ፡ ምድር ፡ ወሰድዋቸው ፡ ከዚያም ፡ በሕግና ፡ በአርነ
ት ፡ ተቀምጠው ፡ ይማሪሉ ፡ በወንጌልም ፡ ተምረው ፡ ወ
ደ ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ይደርሳሉ ፡፡

መክፈል ፡፡ በሰሜን ፡ በመኻከለኛም ፡ በደቡብም ፡ አ
ፍሪቃ ፡ ትከፈላለች ፡፡

## ፩፡፡ የሰሜን ፡ አፍሪቃ ፡፡

### 1. ምሥር ፡ ወይስ ፡ ግብጽ ፡፡

ስ ፡፡ ወ ፡፡ ታት ፡፡ ርት ፡ ፳፱°፡ — ፴፬°፡፡ ወድ ፡ ፳፬°፡ — ፵፪°፡፡
ወደ ፡ ሰ ፡ በመኻከለኛ ፡ ባሕር ፡ ወደ ፡ ምቅ ፡ በስዌጽ ፡ ኢስ
ትሞስና ፡ በኤርትሪ ፡ ባሕር ፡ ወደ ፡ ደ ፡ በኑቢያ ፡ ወደ ፡ ም
ብ ፡ በሊቢያና ፡ በበርካ ፡ ምድረ ፡ በደ ፡ ተወሰነች ፡፡ ስፋት
ዋም ፡ ፲፱፻፻፡ ሚላ ፡ ነው ፡፡

የምድር ፡ ጠባይ ፡፡ ክሊማ ፡ ይተኩሳል ፡ በክረምት
ም ፡ ብቻ ፡ መኻከለኛ ፡ ነው ፡፡ ኻምሲንም ፡ የሚሉት ፡ ት
ኩስ ፡ ንፋስ ፡ ከፈሲካ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ጰራቅሊጦስ ፡ ድ
ረስ ፡ ይነፋሳል ፡ አየርንም ፡ ይጉደል ፡፡ ምድርም ፡ በኒል ፡
ወንዝ ፡ ደር ፡ ሁሉ ፡ እጅግ ፡ ፍርያም ፡ ናት ፡ እጅግም ፡ ተሰ
ሪች ፡፡ ከዚህ ፡ ሌለ ፡ ግን ፡ አሸዋ ፡ ናት ፡፡ አያሌ ፡ መስኖች ፡
ተቈፈሬ ፡ የኒልን ፡ ውኃ ፡ በምላት ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ስፍሪ ፡ ሁ
ሉ ፡ ለማድረስ ፡፡ ዝናም ፡ በምሥር ፡ አይወርድምና ፡ ከሀ
በሻና ፡ ከመኻከለኛ ፡ አፍሪቃ ፡ የሚመጣ ፡ ከመስከረም
ም ፡ ጀምሮ ፡ የሚመላ ፡ ኒል ፡ ምድርን ፡ ያጠጣል ፡፡

ምድር ፡ የምታወጣ ፡፡ እጅግ ፡ እህል ፡ እጅግም ፡ የል
ዩ ፡ ልዩ ፡ አይነት ፡ አታክልት ፡ ጥጥም ፡ ከነቢስም ፡ ተልባ
ም ፡ ሡክርም ፡ ሙጫም ፡ መድኃኒትም ፡ ሀርም ፡፡ እጅግ ፡
ላምም ፡ በግም ፡ ነብም ፡ ፈረስም ፡ አህያም ፡ በቅሎም ፡ ገ

መልም ፡ አራዊትም ፡ ዶፍም ፡ ዓሣም ። ኢብነ ፡ በረደም ፡ ኒ ትረምም ፡ ደንም ፡ ጭውም ።

የ፮ ፡ ስራና ፡ መሻየጥ ፡ አያሌ ፡ ነው ። ቁማሽ ፡ በፍታ ም ፡ ቍርበትም ፡ ብርጭቆም ፡ የሸህላ ፡ እቃም ፡ ነፍጥም ፡ መድኀኒትም ። ለመሻየጥ ፡ የሚበልጡ ፡ የምሥር ፡ አገሮ ች ፡ እሌህ ፡ ናቸው ። መሥር ፡ አስክንድርያም ፡ ደሚያጥ ም ፡ ስዌጽም ።

ባላገሮች ፡ ፫፤ ወይስ ፡ ፬፤ ሚልዮን ፡ ሰዎች ፡ ናቸው ። እ ርሳቸውም ፡ ዐረቦች ፡ ግብጾችም ፡ ቱርኮችም ፡ ሶርያውያን ም ፡ ረሞችም ፡ አርመኖችም ፡ ፍርንጆችም ፡ አይሁድም ። የመንግሥትም ፡ አምልኮ ፡ የእሥላሞች ፡ አምልኮ ፡ ነው ፡ ከዚያም ፡ ሌለ ፡ የክርስቲያንና ፡ ያይሁድ ፡ ማምለክ ፡ ኢ የሥርዓቱ ፡ ይደረጋል ። የወንጌልም ፡ መለክተኞች ፡ አሸክ ሮችን ፡ በወንጌል ፡ ያስተምራሉ ። የምሥር ፡ ገዢም ፡ እር ሱም ፡ ሙሀመድ ፡ ዓሊ ፡ ባሻ ፡ ለወታደሮቹ ፡ የፍርንጆችን ፡ መምህራን ፡ አደረገላቸው ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ በፍርንጆች ፡ ብል ሃትና ፡ እውቀት ፡ የሚያስተምርዋቸው ።

የመንግሥት ፡ መግዛት ፡ በባሻ ፡ እጅ ፡ ነው ። እርሱ ም ፡ ለቱርክያ ፡ ሥልጣን ፡ ይገበራል ። የፍርንጆችንም ፡ ሥ ርዓት ፡ ለሥራዊቱ ፡ አድርጓልና ፡ እጅግ ፡ በረታ ፡ ራሱን ም ፡ መንገሥ ፡ ይፈልጋል ። አያሌ ፡ ጊዜም ፡ ከጌታው ፡ ከ ቱርክያ ፡ ሥልጣን ፡ ጋራ ፡ ተጸላ ፡ ፍርንጆች ፡ ግን ፡ ሥልጣን ን ፡ እንደያጠፋ ፡ ይከለክሉታል ። ያለዚያ ፡ እርሱ ፡ የቱርክ ያን ፡ መንግሥት ፡ አያሌ ፡ ጊዜ ፡ ቢገለብጥ ፡ ነበረ ። ወታደሮ ቹ ፡ ሁሉ ፡ ምናልባት ፡ ፲፻፻፤ ያህላሉ ። በርሳቸው ፡ ኀይል ፡ ከእግዚአብሔር ፡ በታች ፡ እርሱ ፡ ግዛቱን ፡ አሰፋ ፡ ከደርፋ ርና ፡ ከፋሶግሉ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ መኻከለኛ ፡ ባሕር ፡ ድረ ስ ፡ ከእስክንድርያም ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ታናሽ ፡ እስያም ፡ ድረስ ። እንግሊዞችም ፡ ባይከለክሉት ፡ ዛሬ ፡ ያበሻውን ፡ መንግሥት ፡ ቢገዛ ። በመንግሥቱ ፡ የሚቀመጡ ፡ ፍርንጆ ች ፡ ግን ፡ አይገዙለትም ፡ ከየቆንሶሎቻቸው ፡ በታች ፡ ናቸ ው ፡ እንጂ ።

የምሥር ፡ መከፈል ። ምሥር ፡ በላይኛ ፡ በመኻከለኛ

ም ፡ በታችኛም ፡ ምሥር ፡ ተከፈለ ። ፳፫፻፡ ከተሞችና ፡ መንደሮችም ፡ አሉባት ።

## ፩፩። ታ ች ኛ ፡ ምሥር ።

እርስዋም ፡ በ፫፡ ክፍል ፡ ተከፈለች ። *a.* ባ ሕ ሪ ደ ያ ፡ በ ምዕራብ ። *b.* ገ ር ቢ ደ ያ ፡ በኒል ፡ በሁለት ፡ እጆቹ ፡ መኻ ከል ። *c.* ሸ ር ቂ ደ ያ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ።

እ ስ ክ ን ድ ር ያ ፡ በመጀመርያ ፡ በታላቅ ፡ እስክንድር ፡ የተሠራች ፡ ብዙ ፡ ጊዜም ፡ የፈረሰች ፡ አሮጊት ፡ ከተማ ፡ በመኻከለኛ ፡ ባሕር ፡ ደር ። የባኽ ፡ መኖርያ ፡ በበጋ ፡ ጊ ዜ ። የሩም ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ መቀመጫ ። ፪፡ መርሶች ። የፈርንጆች ፡ ቆንሱሎችም ፡ ያለቀቻቸው ፡ መኖርያ ። የጶ ምጴዩስ ፡ ዓምድ ። የክልዮጳትራም ፡ ሃወልት ። እጅግ ፡ መሻየጥ ።

ደ መ ን ኩ ር ፡ የጥጥ ፡ ገቢያ ።

አ ቡ ኪ ር ። የጾር ፡ ማስተማርያ ። ባመት ፡ ፲፯፺፰፡ እን ግሊዞች ፡ ከዚህ ፡ ድል ፡ ነሡ ፡ በፈረንሲሶች ፡ ላይ ።

ረሺ ድ ፡ በኒልና ፡ በመኻከለኛ ፡ ባሕር ፡ ደር ፡ ፳፲፱፡ ሰዎ ች ። የጥጥ ፡ የቁማሽም ፡ የዘይትም ፡ መስሪዮች ።

በዚች ፡ ክፍልም ፡ የ መ ቃ ር ዮ ስ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ አለ ች ፡ የግብጾች ፡ ገዳም ። የናትረም ፡ ባሕርም ። መ ሀ ላ ፡ ክ ቢ ራ ፡ የቁማሽና ፡ የሰልሚያክ ፡ ገቢያ ።

ደ ሚ ያ ት ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ። ፳፻፬፡ ሰዎች ። መርስ ። መ ን ዛ ሌ ፡ እጅግ ፡ መስሪዮች ።

## ፪፪። መ ኻ ከ ለ ኛ ፡ ም ሥ ር ።

መ ሥ ር ፡ ወይስ ፡ መ ሥ ረ ል ቃ ሂ ራ ፡ ወይስ ፡ ቃ ሂ ራ ፡ ወ ይስ ፡ ቃ ይ ሮ ። ይህች ፡ ከተማ ፡ ከአፍሪቃ ፡ ከተሞች ፡ ሁ ሉ ፡ የምትበልጥ ፡ ናት ። ፳፻፱፻፡ ሰዎች ። የባኽ ፡ መኖርያ ፡ በክረምት ። ብርቱ ፡ አምባ ። የግብጾችም ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ መቀመጫ ። ፫፻፡ መስጊዶች ፡ ለእሥላሞች ፡ አያሌ ፡ አብ ያተ ፡ ክርስቲያናትና ፡ ገዳሞችም ፡ ለክርስቲያን ። የወንጌ ልም ፡ መለክተኞች ፡ አሉ ፡ ብዙ ፡ አሽክሮችን ፡ የሚያስተ

ምሩ ፡ እርሳቸውም ፡ እሥላሞችንና ፡ ክርስቲያንን ፡ ሴቶ ችንም ፡ ወንዶችንም ፡፡ አያሌም ፡ የወታደር ፡ ማስተማርያ ች ፡ አሉ ፡ የፈረንጆች ፡ መምህራን ፡ የፈረንጆችን ፡ ብልሃት ና ፡ እውቀት ፡ የጾርንም ፡ ሥርዓት ፡ ወደሚያስተምሩባቸ ው ፡፡ መሥርም ፡ ለሥላሞች ፡ የከበረች ፡ ከተማ ፡ ናት ፡ የው ቀታቸው ፡ መሰብሰቢያ ፡ ናትና ፡፡ ብዙ ፡ መስሪዮችም ፡ ታላ ቅ ፡ ገቢያም ፡፡ የሮደ ፡ ደሴት ፡ በኒል ፡፡ የኒልም ፡ መልከክ ያ ፡፡ የሄልዮጶሊስ ፡ ሃውልትም ፡፡ ጊዛ ፡ መንደር ፡ በኒል ፡ ደር ፡፡ ከዚያም ፡ የድሮ ፡ ጲራሚዶች ፡ ወደስ ፡ አህራም ፡፡ ከዚያ ፡ የመምፌስ ፡ ፍራሾች ፡ ይቀርባሉ ፡፡ ስዌስ ፡ በኤ ርትራ ፡ ባሕር ፡ ማለቅያ ፡፡ የመርከቦችና ፡ የመኻዮጥ ፡ ስፍ ራ ፡፡ የእሥራኤል ፡ ልጆች ፡ በድሮ ፡ ዘመን ፡ ከምሥር ፡ ወ ጥተው ፡ ኤርትራን ፡ የተሻገሩበት ፡ ስፍራ ፡ ቀርብ ፡ ነው ፡፡

ፈዩም ፡ አያሌ ፡ መስሪዮች ፡፡ ምድርም ፡ ከዚህ ፡ እጅ ግ ፡ ሁብታም ፡ ናት ፡፡ የዮሴፍ ፡ መስኖ ፡፡ መንፈሉት ፡ የቁ ማሽና ፡ የህል ፡ ገቢያ ፡፡

፳፫፡፡ ላይኛ ፡ ምሥር ፡፡

ጊርጌ ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ፡፡ ስዩት ፡ ታላቅ ፡ ከተማ ፡፡ የግብ ጾች ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ መቀመጫ ፡፡ በተራሮችም ፡ ብዙ ፡ ዋሾ ች ፡ ተሰሩ ፡፡ እጅግ ፡ መኻዮጥ ፡፡

አኽሚም ፡ ደህና ፡ ከተማ ፡፡ የግብጾች ፡ ቤት ፡ ክርስቲ ያንና ፡ ኤጲስቆጶስ ፡፡

ሉክሶር ፡ ደንድራም ፡ ከርነክም ፡ ቴብንም ፡፡ የድሮ ፡ ታላቅ ፡ ከተማ ፡ ፻፤ ደጆች ፡ የነበሩላት ፡ የቴብን ፡ የሚያደ ንቁ ፡ ፍራሾች ፡ አሉ ፡፡

አስዋን ፡ የኒል ፡ ፏዋፏዌ ፡፡ እድፉ ፡ የአጶሊኖጶሊስ ፡ ፍራሾች ፡ ይቀርባሉ ፡፡ ኬኔ ፡ ገቢያ ፡፡ ቀሰደር ፡ በኤርትራ ፡ ደር ፡፡ መርስ ፡፡ መሻገርያ ፡ ወደ ፡ ዐረብ ፡ ምድር ፡፡

ለምሥር ፡ ባሻም ፡ ለሙሀመዱ ፡ ዓሊ ፡ ብዙ ፡ ሌላ ፡ ግዛ ት ፡ አለው ፡፡ ዛሬ ፡ የሚገዙለትም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ፲፯፤ ሚ ልዮን ፡ ያህል ፡ ያሆናሉ ፡፡

2. በርባርያ ፡ የበርበሮች ፡ ምድር ፡፡

ስ ፡፡ ወ ፡፡ ቷት ፡፡ በርባርያ ፡ ማለት ፡ የሰ ፡ አፍሪቃ ፡ ደር ቻ ፡ ሁሉ ፡ ነው ፡፡ ርት ፡፡ ከምዕብ ፡ ርት ፡ ከ ፲° ጀምሮ ፡ እስ ከ ፡ ምቅ ፡ ርት ፡ እስከ ፡ ፳፯° ድረስ ፡፡ ወደ ፡ ፳፫° — ፴፯°፤ ወደ ፡ ምቅ ፡ በምሥር ፡ ወደ ፡ ደ ፡ በሣሃራ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወደ ፡ ሰ ፡ በመኻከለኛ ፡ ባሕር ፡ ወደ ፡ ምዕብ ፡ በአትላንቲ ስ ፡ ውቅያኖስ ፡ ተወሰነች ፡፡ ርትዋም ፡ ፪፻፡፡ ወርድዋም ፡ ባ ንደንድ ፡ ስፍራ ፡ ፫፻፡፡ ሚላ ፡ ነው ፡፡

የምድር ፡ ጠባይ ፡፡ የአትለስ ፡ ተራሮች ፡ አሉ ፡ በላያ ቸውም ፡ ይበርዳል ፡፡ በባሕር ፡ ደርም ፡ ክሊማ ፡ መኻከለ ኛ ፡ ነው ፡፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ይተኰሳል ፡፡ ምድር ም ፡ በብዙ ፡ ስፍራ ፡ አሸዋ ፡ ናት ፡፡ በወንዞች ፡ አቅራቢያ ና ፡ በባሕር ፡ ደር ፡ ብቻ ፡ ፍርያም ፡ ናት ፡፡

ምድር ፡ የምታወጣ ፡፡ ፍሬ ፡ ወደሚበቍልበት ፡ ስፍ ራ ፡ ደህ ፡ ይገኛል ፡፡ እህል ፡ ከነቢስም ፡ ቶምበኮም ፡ ተም ርም ፡ ዘይትም ፡ የዛፍ ፡ ፍሬም ፡፡ ደህና ፡ ፈረስም ፡ አህያ ም ፡ በቅሎም ፡ ገመልም ፡ በግም ፡ ፍየልም ፡ ዝንጅሮም ፡ አንበሳም ፡ ነምርም ፡ ሰጐንና ፡ ሌላ ፡ ዖፍም ፡ እባብም ፡ ዓሣም ፡፡ ብረትም ፡ እርሳስም ፡ ቀርቀሮም ፡ ብረትም ፡ ደ ንም ፡ ጨውም ፡ ኖራም ፡ የሚነራል ፡ ምንጮችም ፡፡

ባላገሮች ፡፡ ፳፫፤ ሚልዮን ፡ ያህል ፡ ይሆናሉ ፡፡ እርሳቸ ውም ፡ በርብሮች ፡ ዐረቦችም ፡ ቱርኮችም ፡ አይሁድም ፡ ኻንክሎችም ፡ ፍርንጆችም ፡፡ ማምለካቸውም ፡ የእሥላ ም ፡ የክርስቲያንም ፡ ያይሁድም ፡ ያረማውያንም ፡ ማ ምለክ ፡ ነው ፡፡ የወንጌልም ፡ መለክተኞች ፡ ከዚህ ፡ ዙረ ው ፡ አይሁድን ፡ ያስተምራሉ ፡፡

መከፈል ፡ በሌህ ፡ መንግሥቶች ፡፡ ትሪብሉስ ፡ ቱኒስ ም ፡ አልጀርስም ፡ ፈስም ፡ መሮኮም ፡ በለዱልገሪድም ፡፡

## ፩፩፤ የትሪብሉስ ፡ ወይስ ፡ ትሪጶሊስ ፡ ግዛት ፡ ከበር ካና ፡ ከፈዛን ፡ ጋራ ፡፡

በምሥርና ፡ በቱኒስ ፡ መኻከል ፡ ናት ፡፡ ርዝመትዋም ፡ ፩፻፡፡ ሚላ ፡ ታህላለች ፡፡

፪፡ ሚልዮን ፡ ያህል ፡ ሰዎች ፡ አሉባት ፡፡ ያገር ፡ ገዢም ፡ ደይ ፡ ይባላል ፡ በስምምም ፡ ለቱርክያ ፡ ሥልጣን ፡ ይገዛል ፡፡ ክርሱ ፡ ጋሪም ፡ የመካሮች ፡ ሸንጎ ፡ ዲዋን ፡ የሚሉት ፡ አለ ፡፡ ምድርም ፡ በሌህ ፡ ፫፡ ክፍሎች ፡ ተከፈለች ፡፡

*a.* ትሪብሉስ ፡፡

ትሪብሉስ ፡ ከተማ ፡ የደይም ፡ የዲዋንም ፡ መኖርያ ፡፡ ፫፼፡ ሰዎች ፡፡ ብዙ ፡ መስሪዮች ፡፡ አያሌ ፡ መኻየጥም ፡፡

*b.* በርካ ፡፡

በርካ ፡ የሰንጀክ ፡ መኖርያ ፡፡ ቁሪን ፡፡ የድሮ ፡ ቂሬኔ ፡ ፍራሾች ፡ ከዚያ ፡ ይገኛሉ ፡፡ በንጋዚ ፡ የድሮ ፡ ቤሬኒኬ ፡፡ ተዮና ፡፡ በሌህ ፡ ፪፡ ስፍሮች ፡ በጎ ፡ መርሶች ፡ አሉ ፡፡ ሺዋ ፡ የቀደም ፡ ኤሞኒዩም ፡፡ ፯፲፻፡ ሰዎች ፡፡

*c.* ፈዛን ፡፡

ባሸዋ ፡ ምድረ ፡ በደ ፡ በመኻከል ፡ ናት ፡፡ ለትሪብሉስም ፡ ትገበራለች ፡፡ ሙርዙክ ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ፡፡ ፯፲፻፡ ሰዎች ፡፡

---

፳፪፡፡ የቱኒስ ፡ ግዛት ፡፡

በትሪብሉስና ፡ በአልጀርስ ፡ በመኻከል ፡፡ ርዝመትዋ ፡ ከሰሜን ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ ፫፻፡፡ ወርድዋም ፡ ከምሥራቅ ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ ፪፻፡፡ ሚላ ፡ ያህላል ፡፡ መግዛትዋም ፡ እንደ ፡ ትሪብሉስ ፡ መግዛት ፡ ናት ፡፡ ፩፡ ሚልዮንም ፡ ያህል ፡ ሰዎች ፡ አሉባት ፡፡

ቱኒስ ፡ ታላቅና ፡ የከበረች ፡ ከተማ ፡፡ ደህና ፡ ገቢያ ፡፡ ደህና ፡ መርስም ፡፡ ፲፭፼፡ ሰዎች ፡ ከርሳቸውም ፡ ፫፼፡ አይሁድ ፡፡ ብዙ ፡ መስሪዮች ፡፡

በርደ ፡ በርቱ ፡ ከተማ ፡ የገዢም ፡ መኖርያ ፡፡

በርሰኽ ፡፡ ከዚህ ፡ የድሮ ፡ ከርታጎ ፡ ፍራሾች ፡፡ ይቀርባሉ ፡፡

ቢዘርታ ፡ ብርቱ ፡ ከተማ ፡፡ ደህና ፡ ገቢያም ፡፡ የድሮ ፡ ኡቲካ ፡ ፍራሾች ፡፡

ጆርታ ፡ ፈሪና ። ደህና ፡ የመድፍ ፡ መቅለጫ ። መርሶ ችም ።

---

## ፹፫። የአልጀርስ ፡ ግዛት ።

በቱኒስና ፡ በመርኮ ፡ በመኻከል ። ርዝመትዋ ፡ ፭፻። ሚላ ። ወርድዋም ፡ ፫፻። ሚላ ። የዚህች ፡ ምድርም ፡ ታላቅ ፡ ክፍል ፡ ካመት ፡ ፲፰፻፴። ጀምሮ ፡ የፈረንሲሮች ፡ ግዛት ፡ ነው ። ፭፤ ወይስ ፡ ፯፤ ሚልዮን ፡ ሰዎች ፡ አሉባት ።

አልጀርስ ፡ ብርቱ ፡ ያመረችም ፡ ከተማ ፡ በባሕር ፡ ደር ፡ ፲፰፻፻፤ ሰዎች ። ብዙ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ መስሪዮችም ፡ የፈሪን ስ ፡ ንጉሥ ፡ የመስለንዮ ፡ መኖርያ ። የኤጲስቆጶስም ፡ መቀመጫ ። እጅግ ፡ መሻየጥ ።

መስከሪ ፡ ያማረች ፡ ከተማ ።

ቆንስታንቲና ፡ ታላቅና ፡ ብርቱ ፡ ከተማ ፡ ፭፲፱፤ ሰዎች ። ኦራን ፡ ብርቱ ፡ ስፍሪ ። ቡጅያ ፡ ከዚያ ፡ የሚቀርቡ ፡ ተሪ ሮች ፡ ብረትን ፡ ያወጣሉ ። ቦና ፡ መርስ ። ደህና ፡ ገቢያ ። አያሌ ፡ መስሪዮችም ።

---

## ፹፬። የፋስና ፡ የመርኮ ፡ መንግሥት ።

ደህች ፡ መንግሥት ፡ ከአልጀርስ ፡ ወደ ፡ አትላንቲስ ፡ ውቅ ያኖስ ፡ ተዘረጋች ። ርዝመትዋም ፡ ከ፯፻። ሚላ ፡ ትበልጣ ለች ። ወርድዋም ፡ ፫፻። ሚላ ፡ ታህላለች ።

ክሊማ ፡ ደህና ፡ ነው ፡ ምድርም ፡ ፍርያም ፡ ናት ፡ ደሩ ፡ ደ ህና ፡ አድርገው ፡ አይሰርዋትም ። የምድርም ፡ ፍሬ ፡ እን ደ ፡ ቀረች ፡ በርባርያ ፡ ነው ። የጅ ፡ ስሪ ፡ የጥጥ ፡ የሀርም ፡ የቈርበትም ፡ ስሪ ፡ ስጀዴም ፡ ሐረፃም ፡ ባሩድም ፡ ክርታ ስም ፡ ነፍጥም ፡ ሌላ ፡ ስሪም ፡ ነው ።

ባላገሮች ፡ ፲፬፤ ሚልዮን ፡ ፫፹፯። ያህላሉ ። እርሳቸው ም ፡ መውሮች ፡ በርብሮችም ፡ ሻንክሎችም ፡ አይሁድም ፡ ፍረንጆችም ፡ ናቸው ። የመንግሥትም ፡ አምልኮ ፡ እሥላ ም ፡ ነው ። ያለርሶም ፡ ያይሁድን ፡ የክርስቲያንንም ፡ ያ ረማውያንንም ፡ ማምለክ ፡ ያመልካሉ ፡ አይነብረታቸው ።

የመንግሥት ፡ መግዛት ፡ በጣም ፡ ሥልጣን ፡ በሚባል ፡ በንጉሥ ፡ እጅ ፡ ነው ፡፡

መክፈል ፡፡ ፩፡፡ ፈስ ፡፡ ፪፡፡ መሮኮ ፡፡ ፫፡፡ የቀረች ፡ ግዛት ፡፡

### *a.* ፈስ ፡ በ፯፤ ግዛት ፡፡

ፈስ ፡ ከተማ ፡ ታላቅ ፡ ገቢያም ፡ እጅግ ፡ ባለጠግነት ፡ ወደለበት ፡ ፹፰፻፻፡፡ ሰዎች ፡፡ ፰፶፡፡ የውኃ ፡ ምንጮች ፡፡ የእሥላሞች ፡ ታላቅ ፡ ማስተማርያ ፡፡ ብዙ ፡ መሰሪዮችም ፡ የሀር ፡ የበግ ፡ ጸጉርም ፡ የቍርበትም ፡ ስራ ፡ የሚሰራባቸው ፡፡

መቂነጽ ፡ ፯፻፻፡፡ ሰዎች ፡፡ በቀደም ፡ የባሕር ፡ ቀማኞች ፡ ስፍራ ፡ ነበረች ፡፡

ተትዋን ፡ ፹፲፻፡፡ ሰዎች ፡፡ እጅግ ፡ መሻየጥ ፡፡

ተንገር ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ፡ የፈርንጆች ፡ ቆንሱሎችም ፡ መኖርያ ፡፡ ፲፰፲፻፡፡ ሰዎች ፡፡

አሌህ ፡ ቦቶችም ፡ ከስጳንያ ፡ በታች ፡ ናቸው ፡፡

ጼውታ ፡ መርስና ፡ ብርቱ ፡ አምባ ፡ በግብሬልታር ፡ ደጅ ፡፡ የኤጲስቆጶስ ፡ መቀመጫ ፡፡

ሜሊልያ ፡፡ ቄለጽ ፡ ደኅመራም ፡፡ ጼኖን ፡ ደቄለጽም ፡፡

### *b.* መሮኮ ፡ በ፰፤ ግዛት ፡፡

መሮኮ ፡ ከተማ ፡፡ የሥልጣን ፡ መኖርያ ፡፡ ፫፻፻፡፡ ሰዎች ፡፡ ከርሳቸውም ፡ ብዙ ፡ አይሁድ ፡፡

ሞገደር ፡ ወይስ ፡ ስዌራ ፡ አዲስ ፡ ከተማ ፡፡ እጅግ ፡ መሻየጥ ፡፡ አጋደር ፡ ወይስ ፡ ሰንታ ፡ ክሩጽ ፡፡ መርስ ፡፡ ታሩደንት ፡፡

### *c.* የቀረች ፡ ግዛት ፡፡

የድሬ ፡ ምድር ፡፡ የኑን ፡ ምድርም ፡፡ የታፌለትና ፡ የሰስግልሚሳም ፡ ግዛትም ፡፡

ታፌለት ፡ የብዙ ፡ ሸሪፎች ፡ መኖርያ ፡፡ የብዙ ፡ ቅፍሎችም ፡ መሰብሰቢያ ፡፡

፳፭፡፡ በለደሊልግሪድ ::

ታላቅ ፡ ምድረ ፡ በደ ፡ ናት ፡ ባንደንድ ፡ ስፍራ ፡ ብቻ ፡ ተ
ምር ፡ የሚበቀልባት :: ባላገሮች ፡ እንደ ያው ፡ በምድረ፡
በደ ፡ ዙረው ፡ ብዙ ፡ እሥላሞችና ፡ ቀማኞች ፡ ናቸው ::

---

3. የሣሃራ ፡ ታላቅ ፡ ምድረ ፡ በደ ::

ካትለንቲስ ፡ ባሕር ፡ እስከ ፡ ምሥርና ፡ እስከ ፡ ኑቢያ ፡ ተ
ዘረጋች :: ርዝመትዋ ፡ ፲፰፻፡፡ ወርድዋም ፡ ፰፻፡፡ ሚላ ፡ ያህ
ላል :: ፴፪፡ አዋሲስ ፡ የሚልዋቸው ፡ ልምልሞች ፡ ቦቶች ፡
ይገኙባታል ፡ እንጆ ፡ ሁሉ ፡ አኸዋና ፡ ደንጊያ ፡ ያረዊትም ፡
መኖርያ ፡ ነው ::

ባላገሮች :: ዓረቦች ፡ ዋድሊሞችም ፡ ለብደስቦችም ፡
ትዋሪኮችም :: ሁላቸው ፡ አሥላሞች ፡ ናቸው ::

የታወቁ ፡ ስፍሮች :: ዘንሀጋ ፡ ጊለታም ፡ ዝወንዚጋም ፡
ካሰርም ፡ ተርጋም ፡ ለምታም ፡ በርድዋም ::

---

4. ባትለንቲስ ፡ ውቅያኖስ ፡ ያሉ ፡ ያፍሪቃ ፡
ደሴቶች ::

፩፩፡ የጶርቱጊሶች ፡ ደሴቶች ፡ ጶርቶ ፡ ሳንቶና ፡ መዴራ ::

በጶርቶ ፡ ሳንቶ ፡ ፲፰፻፡፡ በመዴራም ፡ ፲፻፻፡፡፡ ሰዎች ፡
አሉ :: በሁለታቸውም ፡ ክሊማ ፡ ደህና ፡ ነው :: ምድርም ፡
እጅግ ፡ ወይንን ፡ እህልንም ፡ ሌላውንም ፡ ደህና ፡ ፍሬን ፡
ደህና ፡ እንጨትንም ፡ ዶፍንም ፡ ታወጣለች ::

ጶርቶ ፡ ሳንቶ ፡ ከተማ :: መርስም ::

ፏንኻል ፡ የመዴራ ፡ ከተማ :: የመስለኒና ፡ የኤጲስቆጶ
ስ ፡ መቀመጫ ፡ ፲፫፲፻፡፡ ሰዎች :: ደህና ፡ ገቢያ ::

መሺኮ ፡ ፪፲፻፡፡ ሰዎች :: ከዚያም ፡ የዴሰርቴስና ፡ የሰልዋ
ግስ ፡ ደሴቶች ፡ ይቀርባሉ ::

---

፪፪፡፡ የአዞሮች ፡ ደሴቶች ::

እርሳቸውም ፡ ፱፡ ናቸው ፡ የጶርቱጋል ፡ ገንዘብ :: ክሊማ ፡

ደህና ፡ ነው ። ምድርም ፡ እጅግ ፡ ታፈራለች ። ባላገሮች ፡ ፲፻፻፡፡፡ ጶርቱጊሶች ፡ ናቸው ።

*a.* ተሬሬ ፡ ፻፻፤ ሰዎች ።

አንገራ ፡ የመስለኒና ፡ የኤጲስቆጶስ ፡ መቀመጫ ። ፯፤ አብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ ፯፤ ገደሞችም ። ደህና ፡ መርስም ።

*b.* ሰንሚጌል ፡ ፶፲፻፡፡፡ ሰዎች ።

ጶንቶ ፡ ደልጋደ ፡ ፲፱፲፻፡ ሰዎች ። አያሌ ፡ መስሪዮችና ፡ መሻየጥም ። ዊላፍረንካ ።

*c.* ሳንታ ፡ ማርያ ፡ ካያሌ ፡ ሌሎች ፡ ደሴቶች ፡ ጋራ ።

---

፳፫፤ የከናርያ ፡ ደሴቶች ።

እርሳቸውም ፡ ፷፤ ናቸው ፡ የስጳኒያ ፡ ግዛት ። ክሊማ ፡ ደተኰሳል ፡ ምድርም ፡ ፍርያም ፡ ናት ። እድግ ፡ እህልም ፡ ደህና ፡ ወደንም ፡ ተልባም ፡ ጥጥም ፡ ሌላ ፡ ደህና ፡ ነገርም ፡ ደወጣባቸዋል ። ባላገሮች ፡ ፷፻፻፡፡፡ ናቸው ። አያሌ ፡ መስሪዮችና ፡ መሻየጥም ፡ አልዋቸው ።

*a.* ከናርያ ፡ ፵፲፻፡፡፡ ሰዎች ።

ቺዊደድ ፡ ደለስ ፡ ጶልማስ ፡ ፱፲፻፡ ሰዎች ። የኤጲስቆጶስ ፡ መቀመጫ ።

*b.* ቴኔሪፋ ፡ ፳፲፻፡፡፡ ሰዎች ። ከዚያም ፡ የታላቅ ፡ ጲክ ፡ ተሪሪ ፡ አለ ።

ሳንታ ፡ ክሩጽ ፡ ፷፲፻፡ ሰዎች ። የመሰለኒ ፡ መቀመጫ ። ቢብልዮቴካም ። ደህና ፡ መርስም ።

አሮታዋ ፡ አያሌ ፡ መስሪዮች ። ለጉና ፡ ፱፲፻፤ ሰዎች ።

*c.* ጰልማ ፡ ፴፲፻፡ ሰዎች ።

*d.* ፏወርት ፡ በንቱሪ ፡ ፱፲፻፡ ሰዎች ።

e. ሬ.ሮ ፡ ፳፲፫፡ ሰዎች ።

ከዚኽ ፡ ደሴትም ፡ ዘንድ ፡ ብዙ ፡ አዋቆች ፡ መሪደ.ያኖች ን ፡ መቍጠር ፡ ይጀምራሉ ።

---

## ፪። መኻከለኛ ፡ አፍሪቃ ።

### 1. ኑቢያ ።

ርት ፡ ፳፫°፡ — ፵°፤ ወድ ፡ ፲፪°፡ — ፳፱°። ወደ ፡ ሰ ፡ በምሥ ር ፡ ወደ ፡ ምቅ ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ ወደ ፡ ደ ፡ በሀበሻ ፡ ወ ደ ፡ ምብ ፡ በኒግሪትያ ፡ ተወሰነች ። ክሊማ ፡ ትኵስ ፡ ነው ። ምድርም ፡ እጅግ ፡ አሸዋ ፡ ናት ፡ በኒል ፡ አጠገብም ፡ ብቻ ፡ ፍርያም ፡ ናት ። በዚኽ ፡ ምድርም ፡ አባይ ፡ ከነጭ ፡ ወንዝ ና ፡ ከተከዜ ፡ ጋራ ፡ ይገናኛልና ፡ ኒል ፡ ይሆናል ።

ምድር ፡ የምታወጣ ። እህል ፡ ወደንም ፡ ሡክርም ፡ ቶምበኮም ፡ መድኃኒትም ፡ ዞጲም ፡ ሌላም ፡ የከበረ ፡ እ ንጨት ፡ ተመርም ፡ ሙጫም ። ላምም ፡ በግም ፡ ደህና ፡ ፈ ረስም ፡ ሰጐንም ፡ ሌላ ፡ ዖፍም ፡ ዝንጀሮም ፡ አራዊትም ። ወርቅም ፡ ብረትም ፡ ጨውም ።

ባላገሮች ። በራበሮች ፡ ኑባም ፡ የዓረብም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ወገኖች ። ቢሸሪንና ፡ አባብደ.ም ፡ ሻንክሎችም ። አምል ካቸውም ፡ የእሥላሞችና ፡ ያረማውያን ፡ አምልኮ ፡ ነው ።

መከፈል ።

#### ፩፩። የኑቢያ ፡ ታላቅ ፡ ውድማ ።

ከዚያ ፡ የበራብራና ፡ ያበብደ ፡ የቢሻሪንም ፡ ሰዎች ፡ ይ ዞራሉ ። በኒል ፡ ደርም ፡ ብዙ ፡ መንደሮች ፡ አሉ ። ያለርሳ ቸው ፡ ግን ፡ ይህች ፡ ምድር ፡ ሀሉ ፡ ምድረ ፡ በደ ፡ ናት ። ወ ደ ፡ ሰ ፡ የክኑስ ፡ ወደስ ፡ የበራብራ ፡ ስፍራ ፡ ነው ። ከዚያ ም ፡ ወደ ፡ ደ ፡ ወጥተህ ፡ ዋደ ፡ ኑባ ፡ ዋደ ፡ ሣልፈም ፡ በጥን ልሀጅርም ፡ ሶኮትም ፡ መሀስም ፡ ይገኛሉ ።

#### ፪፪። የቁርክ ፡ ኑቢያ ።

እርስዋ ፡ በኒልና ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ በመኻከል ፡ ተዘረ

ጋች :: ስዋክን : ደህና : ገቢያ : ለኤርትራ : ደርቻ : በምት
ቀርብ : ደሴት :: ደችም : ክፍል : በጀ : ትባላለች ::

፲፲:: ደንጎላ :: ከተማዋም : ደንጎላ : ናት ::

፩፩:: አትባራ : በአባይና : በተከዜ : በታላቅ : ኒልም :
በመኻከል : ያለች : ጴኒንሱላ ::

፪፪:: ደርኪን : በተከዜና : በመረብ : መኻከል ::

፫፫:: ሰናር :: በቀድሞ : ታላቅ : መንግሥት : ነበረች : ዛሬ :
ግን : የሙሀመድ : ዓሊ : ግዛት : ናት ::

ሰናር : በአባይ :: በቀድሞ : የሰናር : ከተማ : ነበረች :: ዛ
ሬ : ግን : ፈርሳ : ትኖራለች : ጥቂት : ሰዎች : ብቻ : ሳሉባት ::
ከርቱም : ከተማ ::

፬፬:: ኮርደፋን :: ዖበይደ : ከተማ ::

፭፭:: ደርፉር ::

ደህች : ምድር : ታላቅ : መንግሥት : ናት : ለራስዋ : የ
ምትኖር :: ስለርስዋ : የታወቀ : ነገር : ጥቂት : ነው ::

---

## 2. ሀበሻ ::

ስ :: ወ :: ታት :: ርት : ፴፫°; — ፵፫°:: ወዶ : ፫°; ፴'; —
፲፮°:: ወደ : ሰሜንና : ወደ : ምዕብ : በኑቢያ : ወደ : ምቅ : በ
ኤርትራ : ባሕር : ወደ : ደ : በጋሎችና : በሀረር : (ሀራርጌ :)
ተወሰነች :: ታላቅነትዋም : ፫፻፶:::: ሚላ : ታህላለች ::

የምድር : ጠባይ :: ክሊማ : ጤና : አየርም : ጽሩ : ነ
ው : ምድርም : በብዙ : ስፍራ : ፍርያም : ናት :: ታላቆች
ም : ተራሮች : አሉ :: ከርሳቸውም : አያሌ : አሌህ : ናቸ
ው :: የስሜን : ተራሮች : አምባ : ሐይ : ለማልሞም : ብዋ
ሂትም : የሚቀረም :: የአድዋ : ተራሮችም : ሰማያታ :
ኪደነ : ምህረትም : ሸሉደም : ኩቢም : የሚቀረም :: ያ
ጋሚ : ተራሮችም : ሀረማት : ደብረ : ደሞም : ረጓያደም :
ካሰልጎም :: የለስታ : ተራሮችም : ላሊበላና : ሌሎች :: የ

ሀላይ ፡ ተራሮችም ፡ ተረንታ ፡ ቮሞሬይቶም ፡ የሰማንርም ፡ ተ
ራሮች ። የቨዋና ፡ የኢፌትም ፡ ተራሮች ፡ እንደ ፡ ብርቱ ፡
አምባ ፡ ደህችን ፡ መንግሥት ፡ ዙረው ፡ የሚያጸኑ ። ወንዞ
ች ። አባይ ፡ ተከዜም ፡ ሀዋሽም ፡ ከብዙ ፡ ታናሾችና ፡ ታላ
ቆች ፡ ወንዞች ፡ ጋራ ፡ በክረምት ፡ መሌተው ፡ ምሥርን ፡
የሚያጠጡ ። ሀዋሽ ፡ ብቻ ፡ ካዜብ ፡ ወደ ፡ መሥእ ፡ ሒደ ፡
በአውሳ ፡ ባደሎች ፡ ምድር ፡ ይቆማልና ፡ አሸዋን ፡ ያጠጣ
ል ። የምድር ፡ ባሕሮች ። የጻና ፡ ባሕር ፡ በደምቢያ ፡ ግ
ዛት ። ያሸንጊ ፡ ባሕርም ፡ በወሬላ ፡ ግዛት ። የሣይክ ፡ ባሕ
ርም ፡ በተሁላደሬ ። የጉራጌ ፡ ባሕሮችም ፡ ዝዋይና ፡ ሌሎ
ች ። አሰልም ፡ የሚባል ፡ የጨው ፡ ባሕር ፡ ባደሎች ፡ ምድ
ር ፡ የሚቀረም ።

ምድር ፡ የምታወጣ ። እጅግ ፡ እህል ፡ እርሾም ፡ ጥቁ
ርና ፡ ነጭ ፡ ስንዴ ፡ ገብስም ፡ ጤፍም ፡ ደጉሳም ፡ አጃም ፡
ማሽላም ፡ ዘንጋደም ፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ ኢደነትም ፡ አታክል
ት ፡ እንደ ፡ አደንጓሬ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ አጥርም ፡ አብሽም ፡ ም
ስርም ፡ ባቄላም ፡ ሽምብራም ፡ ተልባም ፡ ኑግም ፡ ጓያም ፡
ጎመንም ፡ ስናፍጭም ፡ ጉልቋም ። ለመድኃኒትና ፡ ለሌላ ፡
ጉደይም ፡ የሚጠቅሙ ፡ አታክልት ። እንደድ ፡ አርግሬሳ
ም ፡ እሬትም ፡ ከሚላም ፡ ጻደም ፡ ጌሾም ፡ እንሴትም ፡
ደረጸትም ፡ ድምብላልም ፡ ሙዝም ፡ አስተናገርም ፡ ቃደ
ና ፡ ነጭ ፡ ቹንጉርትም ፡ ጨጎነትም ፡ ጽላል ፡ ማርያምም ፡
ትርናሣም ፡ ብርብራም ፡ ጤናደምም ፡ አፍርንጅም ፡ ምጪም
ጬም ፡ ቡንም ፡ ጫድም ፡ ቶምበኾም ፡ የመስቀል ፡ አበባ
ም ፡ ስዋርያም ። የብዙ ፡ አደነት ፡ ዛፍም ፡ እንደ ፡ ወርካ ፡
ቍልቋልም ፡ ጵድም ፡ ዋንዛም ፡ ወደራም ፡ ግራርም ፡ ጼዴ
ኖም ፡ ኮኽም ፡ ቆሮም ፡ ረማንም ፡ ሎሚንም ፡ ምሰናም ፡
የዝንጅር ፡ ወንበርም ፡ ዞጲም ፡ አሽከላም ፡ አፃብአልም ፡
ጅባርዋም ፡ ድማም ፡ አስታም ፡ ትረንጊም ፡ የብዙ ፡ ሌላ ፡
አደነትም ፡ እንጨት ። ፈረስም ፡ በቅሎም ፡ አህያም ፡ ላ
ምም ፡ ነሽም ፡ በግም ፡ ፍየልም ፡ ዝብራም ፡ ምደቋም ፡
ብሆርም ፡ ሣሳም ፡ ብእዛም ፡ መንትሌም ፡ ጠንቸልም ፡
አገዜንም ፡ ውድምቢም ፡ ጥልያም ፡ ቀልበዴም ፡ ዲኩላ

ም ፡ (ጎማ ፡) ወደልሊም ፡ ቅንፎዝም ፡ ድፊሳም ፡ ጅራት ፡ ቀጭንም ፡ እርያም ፡ ሀሰማም ፡ ተኵላም ፡ ውሻም ፡ ቀበሮ ም ፡ ጅብም ፡ ነብርም ፡ አንበሳም ፡ ጽሔራም ፡ አውራሪስ ም ፡ ዝሆንም ፡ ዝንጅሮም ፡ ጦታም ፡ አሽቆቆም ፡ ሙጭል ጭላም ፡ ግሥላም ፡ ዋረቦም ፡ ዝባድም ፡ ጉሬዛም ፡ የም ስክ ፡ አደጥም ፡ ፈርዋም ፡ የውኃ ፡ ውሻም ፡ ጉማሬም ፡ አዞም ፡ ጉልጉል ፡ ነምርም ፡ ጬኾምበሳም ፡ ተትጊም ፡ እባ ብም ፡፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ አይነትም ፡ ዎፎች ፡ ከርሳቸውም ፡ ብዙ ፡ አሞራ ፡ እንደ ፡ ነስር ፡ ነስር ፡ ወርቅም ፡ ፈረስ ፡ ሰደጣን ም ፡ እርኮምም ፡ ደብራም ፡ ዝደም ፡ ርግብም ፡ ህምህም ም ፡ ዋልያም ፡ ቁምሬም ፡ ግድግድም ፡ ጉጊም ፡ ነጭ ፡ አሞ ራም ፡ ገምብም ፡ ቆቅም ፡ ዝግራም ፡ የውኃ ፡ ደሮም ፡ ሬዛ ም ፡ ጢጦም ፡ በቋልም ፡ እምባላም ፡ እንድርማሚቱም ፡ ጭርናም ፡ ቁራም ፡ የመስቀል ፡ ዎፎም ፡ ሰጐንም ፡ ዋሪም ፡ ጉሪማደሌም ፡ ዋስም ፡፡ ዓሣም ፡፡ ወርቅም ፡ እጅግ ፡ ብረ ትም ፡ እጅግ ፡ ጭውም ፡ ባርሆ ፡ ሚደና ፡ በአሰል ፡ ባሕር ፡ ባደሎች ፡ ምድር ፡ መግዣ ፡ የሚሆን ፡፡

የጅ ፡ ስራ ፡ ጥቂት ፡ ነው ፡፡ ስለዚህም ፡ ባላገሮች ፡ ድኆ ች ፡ ናቸው ፡፡ ስራውን ፡ ቢሰሩ ፡ ምድራቸው ፡ ነገርን ፡ ሁሉ ን ፡ ብትሰጥ ፡ ነበር ፡፡ ያበሻ ፡ ሰዎች ፡ የስራውን ፡ ደህንነት ና ፡ በረከት ፡ አያውቁምና ፡ ሀኬትንና ፡ ጨወታውን ፡ ደወደ ሉ ፡ ከስራ ፡ ደልቅ ፡ ስለዚህም ፡ ኃጢአትና ፡ መከራ ፡ በዛባ ቸው ፡፡ የሚሰራ ፡ ስራ ፡ ደህ ፡ ነው ፡፡ ሸማ ፡ ባምኃራና ፡ በ ትግሬ ፡ እሥላሞች ፡ በሸዋም ፡ ክርስቲያኖችም ፡ ደሰሩታ ል ፡፡ ብረትም ፡ የፈላሾችና ፡ የጠቢባን ፡ ስራ ፡ ያለ ፡ የሌሎ ችም ፡ አንጥረኞች ፡፡ ሌላም ፡ የሚሰራ ፡ ስራ ፡ ደህ ፡ ነው ፡፡ የሸህላ ፡ የቀንድም ፡ የንጨትም ፡ የሣዕርም ፡ ስራ ፡ ሐረ ፃም ፡ ሌማትም ፡ (ገበታ ፡) የቆርበትም ፡ ስራ ፡ የሚቀርም ፡፡

ያበሻም ፡ መሻየጥ ፡ ጥቂት ፡ ነው ፡፡ የብርና ፡ የወርቅ ፡ የነሣስም ፡ መግዣ ፡ በዚች ፡ ምድር ፡ የሚቀረጽ ፡ የለም ፡፡ በመሻየጥ ፡ ሁሉ ፡ የሚለወጥ ፡ ብር ፡ ያንድ ፡ አይነት ፡ ብ ቻ ፡ ነው ፡ ያውስትርያ ፡ ንግሥት ፡ የማርያም ፡ ትሬስያ ፡ ቅ ርጽ ፡ ብቻ ፡ አንስት ፡ ብር ፡ የሚባል ፡፡ ከዚያ ፡ ሌላም ፡ መ

ግዛቸው ፡ ልውጥ ፡ እቃ ፡ ነው ፡ እንደ ፡ ጨው ፡ ሸማም ፡ እ
ህልም ፡ ሌላ ፡ እቃም ፡፡ ወደ ፡ እንግደ ፡ አገርም ፡ የሚሻየ
ጥ ፡ ሁሉ ፡ በቅፎለቶች ፡ ይሻየጣል ፡፡ ሸያጩም ፡ ይህ ፡
ነው ፡፡ ባሮች ፡ አባቅልቶችም ፡ የዝሆን ፡ ጥርስም ፡ እህል
ም ፡ ጥቂት ፡ ሸማም ፡ ቡንም ፡ ዝባድም ፡ ዝንጅብርም ፡
መስክም ፡ ሌላ ፡ ሽቱም ፡ እጣንም ፡ ከርቤም ፡ ጥቂት ፡ ወ
ርቅም ፡፡ ከሌላ ፡ አገርም ፡ የሚገባ ፡ ሸያጭ ፡ ይህ ፡ ነው ፡፡
ቅርሽ ፡ ሀርም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ልብስም ፡ ሶሬትም ፡ ስንካንም ፡
ብርብሪም ፡ መርፌም ፡ መቀስም ፡ መቍረጫም ፡ አጅም ፡
ሌላ ፡ እቃም ፡፡

ባላገሮች ፡፡ ቍጥራቸው ፡ አልታወቀም ፡፡ ያበሻ ፡ ስዎች ፡
በደርቻቸው ፡ ከሚኖሩ ፡ አሕዛብ ፡ ከጋሎችና ፡ ካደሎች ፡ ከ
ጉራጌም ፡ ከናርያም ፡ ከከፋም ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ ምናልባት ፡
፯፡ ሚልዮን ፡ ያህላሉ ፡፡ እርሳቸውም ፡ የያሌ ፡ አይነት ፡ ና
ቸው ፡፡ አይነተኞች ፡ ሀበሻውያን ፡ ወይስ ፡ ኢትዮጵያውያን ፡
በትግሬ ፡ ባምኃራም ፡ በሸዋም ፡ ይቀመጣሉ ፡፡ ፈላሾችም ፡
ያይሁድ ፡ ወገን ፡ በስሜን ፡፡ አደሎችም ፡ እርሳቸውም ፡
ደናኪል ፡ የተባሉ ፡፡ ጋሎችም ፡ የሚቀሩም ፡ አሕዛብ ፡ በየ
ምድራቸው ፡፡

ያበሻ ፡ ሰዎች ፡ አምልኮ ፡፡ የሰው ፡ ወገን ፡ ልዩነት ፡ ባ
በሻ ፡ እንደ ፡ በዛ ፡ እንዲህም ፡ በዛ ፡ ያምልኳቸው ፡ ልዩነት ፡፡
ባምልኳቸውም ፡ የታወቁ ፡ ክርስቲያን ፡ እሥላሞችም ፡
አይሁድም ፡ ከማውንትም ፡ ዘላኖችም ፡ አረማውያንም ፡
ናቸው ፡፡ አሁንም ፡ ጳውሎስ ፡ እንደለ ፡ ያቴናን ፡ ሰዎች ፡
ባርዮስ ፡ ፋጎስ ፡ ሁኖ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ እግዚአብሔር ፡ ፈ
ጠረ ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉን ፡ካንድ ፡ ሰው ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፡ በ
ምድር ፡ ፊት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡፡ ጊዜውንም ፡ ዘመኑንም ፡ ሰራ
ላቸው ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ስፍራቸውንም ፡ ይኖሩበት ፡ ዘን
ድ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዲሹ ፡ እንዲፈልጉትም ፡ ምናል
ባት ፡ ያገኙት ፡ እንደሆን ፡፡ እንዲሁም ፡ እግዚአብሔር ፡ በ
ጥበቡ ፡ በፍቅሩም ፡ ለሌህ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ አሕዛብ ፡ ጉልታቸ
ውን ፡ ከሀበሻ ፡ ክርስቲያን ፡ ጋራ ፡ አደረገ ፡ የክርስቲያንን ፡
አምላክ ፡ ይሹ ፡ ዘንድ ፡፡ ለክርስቲያንም ፡ ሁሉ ፡ ተገብቶ

ዋልና ፡ ባልንጀራውን ፡ ማለት ፡ ሰውን ፡ ሁሉን ፡ እንደ ፡ ነ
ፍሱ ፡ ይወድ ፡ ዘንድ ፡ ላበሻ ፡ ክርስቲያንም ፡ ይገባል ፡ በዙ
ርያቸውና ፡ በመኻከላቸው ፡ ያሉትን ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ደ
ህንነታቸውን ፡ እንዲሹ ፡ በወንጌልም ፡ እንዲያስተምርዋቸ
ው ፡ የሣይማናትንም ፡ መንገድ ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ደህንነት ፡
የሚወስደውን ፡ እንዲያሳይዋቸው ። ያም ፡ ባይሆን ፡ እል
ያ ፡ አሕዛብስ ፡ በኃጢአታቸው ፡ ይጠፋሉ ። እግዚአብሔር ፡
ግን ፡ መጥፋታቸውን ፡ ክርስቲያን ፡ በተባሉ ፡ ይቈጥራል ።
ይህንንም ፡ ፈርተው ፡ በምዕራብ ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡
ማኽል ፡ ያለች ፡ የሚስዮን ፡ ጉባኤ ፡ የሕይወትን ፡ ቃል ፡ ባ
ምኃርኛ ፡ ቋንቋ ፡ ተተርጕሞ ፡ በመልክተኞቻቸው ፡ እጅ ፡ ይ
ሰዲላቸዋል ፡ የወንድሞቻቸውን ፡ የክርስቲያንን ፡ ልብ ፡
በክርስቶስ ፡ እውቀትና ፡ ጸጋ ፡ ያጸኑ ፡ ዘንድ ፡ ያስነቋቸው
ም ፡ ዘንድ ፡ የወንጌልን ፡ ብርሃን ፡ በጨለማ ፡ በሚቀመጡ ፡
ወንድሞቻቸው ፡ ባረማውያን ፡ መኻከል ፡ ለመዘረጋት ።
እግዚአብሔር ፡ ያበሻ ፡ ክርስቲያንን ፡ ዓይን ፡ ይክፈት ፡ ይህ
ነን ፡ ፍቅር ፡ የእግዚአብሔርም ፡ የጸጋውን ፡ ወሬት ፡ ዝምብ
ሎ ፡ እንደይቈጥሬት ፡ ለደህንነታቸው ፡ የሚጠቅመውን ፡
በዚች ፡ ጊዜያቸው ፡ እንዲያስቡት ፡ እንጅ ።

ያበሻ ፡ ምድር ፡ መግዛት ።

ሀበሻ ፡ በቀደም ፡ አንዲት ፡ ታላቅ ፡ መንግሥት ፡ ነበረች ።
ዛሬ ፡ ግን ፡ በሁለት ፡ መንግሥቶች ፡ ተከፈለች ። ያለርሳቸ
ውም ፡ አያሌ ፡ ሌሎች ፡ ምድሮች ፡ አሉ ።

## ፩፩። የጎንደር ፡ መንግሥት ።

የዚች ፡ መንግሥት ፡ ንጉሥ ፡ በስም ፡ ብቻ ፡ ይገዛል ። ኃይ
ሉ ፡ ራስ ፡ ወደሚሉት ፡ ወደ ፡ መጀመርያ ፡ አለቃው ፡ እጅአ
ለፈ ። ይች ፡ መንግሥትም ፡ በሁለት ፡ ታላቆች ፡ ክፍሎች ፡
በአምኃራና ፡ በትግሬ ፡ ተከፈለች ። የተከዜም ፡ ወንዝ ፡
በመኻከላቸው ፡ ፈሶ ፡ ሁለታቸውን ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡
ይለያቸዋል ።

### A. የአምኃራ ፡ ምድር ።

*a.* የደምቢያ ፡ ግዛት ።

ጎንደር ፡ የመንግሥት ፡ ሁሉ ፡ ከተማ ፡ የንጉሥም ፡ መ ኖርያ ። የአቡንና ፡ የእጨጌ ፡ መቀመጫ ። ዛሬ ፡ ግን ፡ ፲፪፤ ሺ ፡ አመት ፡ አቡን ፡ ታጣ ። ታላቅና ፡ ደሀና ፡ ገቢያ ። የንጉሥ ፡ ግምብ ። ፶፻ ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናትም ። ከዚያም ፡ ቁ ስቋምና ፡ ደብረ ፡ ፀሓይ ፡ ደቀርባሉ ።

ጨልጋ ፡ ታላቅ ፡ አገርና ፡ ገቢያ ። ወኅኔ ፡ ገቢያ ፡ በኑቢ ያ ፡ ወሰን ። ወርቅሌባ ። እሥላምጌ ፡ የሥላሞች ፡ ሰፈ ሬ ፡ በጎንደር ፡ አጠገብ ።

አቡና ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ታላቅ ፡ አገርና ፡ ገደም ። ደንቅዝ ። ኪደነ ፡ ምሀረት ፡ ታላቅ ፡ አገር ። ድንግልበ ር ፡ ታላቅ ፡ አገር ፡ በጻና ፡ ደር ። ከዚያ ፡ እጅግ ፡ ወይን ፡ ደ ወጣል ።

ፈርቃ ፡ ወደስ ፡ ደለቍስ ፡ ከዚያ ፡ አባይ ፡ ወደ ፡ ጻና ፡ ባ ሕር ፡ ደገባል ። እምፈራስ ፡ ታላቅ ፡ አገር ። የንጉሥ ፡ ግ ምብ ። ታላቅ ፡ ገቢያ ።

*b.* የፎገራ ፡ ግዛት ። ከደምቢያ ፡ ታንሳለች ።

ላምጌ ። ናበጋም ፡ መንደሮች ። የርብ ፡ ወንዝ ፡ ከዚ ያ ፡ ወደ ፡ ጻና ፡ ደገባል ። ልበቅ ፡ የትኵስ ፡ ውኃ ፡ ምንጮ ች ። ድሬ ፡ ታላቅ ፡ አገር ።

*c.* የበገምድር ፡ ግዛት ።

ደብረ ፡ ታቦር ፡ ከተማ ፡ የራስም ፡ መኖርያ ።

ማኅደረ ፡ ማርያም ፡ ታላቅ ፡ አገር ። ጉና ፡ በገምድ ር ፡ ታላቅ ፡ አገርና ፡ ግዛት ።

*d.* የጎጀም ፡ ግዛት ፡ ታላቅ ፡ ናት ። አባይ ፡ ከዚህ ፡ ደመ ንጪል ።

ሞጣ ፡ ታላቅ ፡ አገር ። ዘዋ ፡ የበቀደም ፡ ከተማ ። ታላ ቅ ፡ አገር ። ቢቸና ፡ ከተማ ። ብሬንታ ፡ በአባይ ፡ ደር ። ደ ማ ፡ የቅዱስ ፡ ጊዎርጊስ ፡ ገደም ። ባሳና ፡ ገቢያ ።

*e.* የበለሳ ፡ ግዛት ።

አቡና ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ። ታላቅ ፡ አገር ።

*f.* የወግራ ፡ ግዛት ። ወግራ ፡ የግብር ፡ ሰፈሬ ።

*g.* የሰሜን ፡ ግዛት ። ወደ ፡ ምሥራቅና ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ በ ተከዜ ፡ ወደ ፡ ምዕራብም ፡ በወልደባ ፡ በጸገደም ፡ በወግሬ

ም ፡ በደምቢያም ፡ ወደ ፡ ደቡብም ፡ በበሎሳ ፡ ተወሰነች ።
ምድርም ፡ ደግኖ ፡ ናት ።

ታላቆች ፡ ተራሮች ፡ አምባ ፡ ሓይ ፡ በየደም ፡ ለማልሞ ም ፡ ብዋሂትም ፡ ናቸው ።

እንጨትካብ ፡ ከተማ ። ሃወዛ ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ። ብዙ ፡ እሥላሞች ። የስሜን ፡ ደጅ ፡ አዝማችም ፡ ዛሬ ፡ ከስሜን ፡ በቀር ፡ በጸገዴ ፡ በወልቃይትም ፡ በወልደባም ፡ ከተከዜ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅም ፡ ባለች ፡ ባበሻ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ደገዛል ።

*h.* የጸገዴ ፡ ግዛት ።

*i.* የወልቃይት ፡ ግዛት ። የሌህ ፡ ሁለት ፡ ግዛቶች ፡ ምድር ፡ ቈላ ፡ ናት ፡ እጅግ ፡ ፍርያምም ። ክሊማ ፡ ግን ፡ ጤና ፡ አይደለም ።

*j.* የወልደባ ፡ ግዛት ፡ የገደሞች ፡ ምድር ።

*k.* የደሞት ፡ ግዛት ። ቡሬ ፡ ከተማ ። ደምበጫ ፡ ገቢያ ።

*l.* የሜጫ ፡ ግዛት ። *m.* የአ.ባባ ፡ ግዛት ። *n.* የአገው ፡ ግዛት ፡ ፳፡ ገዦች ፡ ያሉባት ።

## ፪፪፡ የትግሬ ፡ ምድር ።

*a.* አይነተኛ ፡ ትግሬ ፡ እርስዋም ፡ የነብሪድ ፡ ግዛት ። ያቡን ፡ ግዛትም ። የአባገሪማ ፡ ግዛትም ፡ አድዋም ፡ ደግናም ፡ የሚቀርም ።

አክሱም ፡ በድሮ ፡ ዘመን ፡ ያበሻ ፡ ሁሉ ፡ ከተማ ። ዛሬም ፡ የነብሪድ ፡ መኖርያ ፡ ናት ። ፫፲፻፡ ወይስ ፡ ፬፲፻፡ ሰዎች ። አደር ፡ ፅዮን ፡ የምትባል ፡ ደህና ፡ ቤተ ፡ክርስቲያን ። ታላቅ ፡ ሃወልትም ፡ ከፍታው ፡ ፵፡ ክንድ ፡ የሚያህል ። ምናልባት ፡ የድሮ ፡ ግብጾች ፡ ስራ ፡ በጵቶልሜዎስ ፡ ኤወርጌቲስ ፡ ዘመን ፡ የተሰራ ። አያሌም ፡ የወደቁ ፡ ሃወልቶች ። አያሌም ፡ ጽሬት ፡ የተወቀረባቸው ፡ ደንጎች ፡ የድሮ ፡ ዘመን ፡ ስራ ።

አድዋ ፡ የትግሬ ፡ ሁለተኛ ፡ ከተማ ፡ ፫፲፻፡ የሚያህሉ ፡ ሰዎች ። ገቢያ ። ፬፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናትም ። የሰማያ

ታም ፡ የአበገሪማም ፡ የኪዳነ ፡ ምሕረትም ፡ የሽሉዲም ፡ የደጦማም ፡ የደብረ ፡ ሲናም ፡ ተራሮች ፡ ይቀርባሉ ::

ማይ ፡ ጉጊ ፡ ለአድዋ ፡ የምትቀርብ :: በፖርቱጊዞች ፡ የተሠራች ፡ የፍሬመንትዮስ ፡ ወይስ ፡ ሬርመናቶስ ፡ ገዳም ፡ ፍሬሞች :: አበ ፡ ገሪማ ፡ ታላቅ ፡ ገዳም ፡ በኪዳነ ፡ መሕረት ፡ አጠገብ :: የድሮ ፡ ፍሬሞችም ፡ አሉ :: ማርያም ፡ ሸዊቶ :: ምምሳሕ :: ዓዲ ፡ አቡን ፡ ያቡን ፡ ቤት ፡ ወደለ ::

ገንደብታ ፡ ታላቅ ፡ አገርና ፡ ግዛት ::

ከዚያም ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ አያሌ ፡ ለብቻቸው ፡ ያሉ ፡ ግዛቶች ፡ ይከተላሉ :: አንቲጬ ፡ ታላቅ ፡ አገርና ፡ ግዛት :: ዓዲ ፡ ቍልፊ ::

የሃ ፡ የድሮ ፡ ፍሬሞች :: መስበር ፡ ዛሬ ፡ የደሆና ፡ ናይብ ፡ ግዛት :: መጋርያ ፡ ጸምሪ :: አገላ ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ :: ዝባንኲላ ::

*b.* አህስኣ ፡ በትግሬና ፡ በመርብ ፡ ወንዝ ፡ በሥራዌም ፡ መኻከል ::

ሐደሽ ፡ ዓዲ ፡ ታላቅ ፡ አገርና ፡ ግዛት ::

*c.* ዓዲ ፡ አርባዕቲ :: *d.* ሥራዌ ::

*e.* ሀመሴን :: የወሰን ፡ ግዛት ፡ ወደ ፡ ሰሜን :: ሾብዓቴ ፡ ቍልፊ ::

ዓዲ ፡ ኂላ ፡ ፪፤ አገሮች ፡ በሻንክሎች ፡ ወሰን ::

*f.* ደቀ ፡ ጉዛይ ፡ ታላቅ ፡ ግዛት ፡ ከሀመሴን ፡ እስከ ፡ አጋሜ ፡ ከሀላይም ፡ እስከ ፡ እግረ ፡ ዝቡእ ፡ የተዘረጋች ::

ድክሳ ፡ ታላቅ ፡ አገር ፡ ክፍልዋ ፡ ለናይብ ፡ የምትገዛ ::

ሀላይ ፡ የወሰን ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ሰምሃር ፡ በቶምፊደቶ ፡ ላይ ፡ የምትኖር :: ማርድኣ :: እግረዝቡእ ፡ የግብር ፡ ስፍራ ::

ሎጎ :: ንጎት :: ማይጸራና :: ዓዲ ቃይሕ :: ቶኾንደ :: ቊላ :: ስናፌ :: ማይቃይሕ :: ቤሓት ::

*g.* አጋሜ :: ደጋ ፡ ናት :: ወደ ፡ ሰ ፡ በደቀ ፡ ጉዛይ :: ወደ ፡ ምቅ ፡ በአርኖና ፡ በተልታሎች ፡ ምድር :: ወደ ፡ ደ ፡ በእንደርታ :: ወደ ፡ ምብ ፡ በተምቤን ፡ በትግሬም ፡ በአንቲጬም ፡ ተወሰነች ::

ዓድ ፡ ግሬት ፡ ከተማ ፡ የደጅ ፡ አዝማችም ፡ መኖርያ ::
ግናተር :: ሀረማት ፡ አያሌ ፡ ታላቆች ፡ ተራሮችና ፡ ብርቶ
ች ፡ አምቦች ::

*h.* እንደርታ ፡ ወደ ፡ ሰ ፡ በአጋሜ ፡ ወደ ፡ ምቅ ፡ በወጅራ
ትና ፡ በወፌላ ፡ ወደ ፡ ደ ፡ በለስታ ፡ ወደ ፡ ምብ ፡ በተከዜና ፡
በተምቤን ፡ ተወሰነች ::

ህንጣሎ ፡ ታላቅ ፡ ከተማና ፡ ገቢያ :: ጨልቁት :: ያመ
ረች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን :: ሳልዋና ፡ ቦሬ ፡ ታላቅ ፡ ግዛት ::
ደጋ ፡ ምድርም :: ግባ ፡ የወሰነ ፡ መንደር ፡ በንደርታና ፡ በተ
ምቤን ፡ መኻከል :: ያሻንጌ ፡ ባሕር ፡ በንደርታና ፡ በለስ
ታ ፡ መኻከል ::

በተከዜም ፡ በምሥራቅ ፡ ደሬ ፡ ያበርጋሌ ፡ ጋሎች ፡ አ
ሉ ፡ ለንደርታም ፡ ደገዛሉ ::

*i.* ወጅራት :: ወደ ፡ ሰ ፡ ወደ ፡ ምብ ፡ በንደርታ ፡ ወደ ፡ ደ ፡
በወፌላ ፡ ወደ ፡ ምቅ ፡ በደብአ ፡ ጋሎች ፡ ተወሰነች ::

*j.* ወፌላ ፡ ወደ ፡ ሰ ፡ በወጅራት ፡ ወደ ፡ ምብ ፡ በንደርታ
ና ፡ በለስታ ፡ ወደ ፡ ደ ፡ በአንጎት ፡ ወደ ፡ ምቅ ፡ በደብኣና ፡ በ
አስቦ ፡ ጋሎች ፡ ተወሰነች ::

*k.* ለስታ ፡ ደጋ ፡ ምድር ፡ ተከዜ ፡ የሚመንጭባት :: በተ
ከዜም ፡ ሁለት ፡ ደሮች ፡ ትኖራለች :: ወደ ፡ ምቅ ፡ ባንጎት ፡
ወደ ፡ ደ ፡ በወጫሌ ፡ ጋሎችና ፡ በየጁው ፡ ወደ ፡ ምብ ፡ በበገ
ምድር ፡ ወደ ፡ ሰ ፡ በበለሳ ፡ በስሜንም ፡ በንደርታም ፡ ተወ
ሰነች ::

ላሊበላ ፡ ከተማ :: የከበረች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ላሊ
በላ ፡ ንጉሥ ፡ በደንጊያ ፡ ያስወቀራት ::

ዓይን ፡ ተከዜ ፡ የተከዜ ፡ ምንጭ ፡ ወደለ ::

*l.* ተምቤን ፡ ወደ ፡ ሰ ፡ በትግሬ ፡ ወደ ፡ ምቅ ፡ በአጋሜና ፡
በንደርታ ፡ ወደ ፡ ደ ፡ በንደርታ ፡ ወደ ፡ ምብ ፡ በተከዜና ፡ በ
ሺሬ ፡ በአዴትም ፡ ተወሰነች :: ጽኣደና ፡ ጋለበደ ፡ መን
ደሮች ::

በተምቤንና ፡ በሺሬ ፡ መኻከልም ፡ የላይኛና ፡ የታችኛ ፡
አዴት ፡ ግዛት ፡ አለች ::

*m.* ሺሬ :: ወደ ፡ ምቅ ፡ በትግሬና ፡ በታችኛ ፡ አዴት ፡ በተ

ምቢንም ፡ ወደ ፡ ደ ፡ ወደ ፡ ምቅ ፡ በተከዜ ፡ ወደ ፡ ሰ ፡ በጎን ክሎች ፡ ምድር ፡ ተወሰነች ። ይህች ፡ ግዛትም ፡ በቀደም ፡ ሰው ፡ መልቶባት ፡ ነበር ። ምድር ፡ ፈርያም ፡ ናትና ። ዛሬ ፡ ግን ፡ አያሌ ፡ አመት ፡ ተቀምጣለችና ፡ አያሌ ፡ ጊዜም ፡ የ ጾር ፡ ስፍራ ፡ ነበረችና ፡ ባድ ፡ ሆነች ።

ጠምብላ ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ። ቍራራ ። ዛና ።

---

ይህች ፡ እነሆ ፡ የጎንደር ፡ መንግሥት ፡ ናት ፡ ዛሬ ፡ እንዳ ለች ። አይነተኛ ፡ አምኃራ ፡ የምትባል ፡ አንጎትም ፡ ዛሬ ፡ የጋሎች ፡ መቀመጫ ፡ ናቸው ፡ ተከፍለው ፡ የሚገበሩ ፡ ወ ደ ፡ ጎንደር ፡ መንግሥት ፡ ግን ፡ የማይቈጠሩ ።

ወደ ፡ ምብ ፡ እሌህ ፡ ግዛቶች ፡ አሉ ። የበሶ ፡ የጎንጋም ፡ የጉድሩም ፡ የቋሪም ፡ ግዛቶች ።

ከሺሬ ፡ ወደ ፡ ሰ ፡ ምስኪኖች ፡ ሻንክሎች ፡ ይኖራሉ ። ወደርሳቸውም ፡ ያበሻ ፡ ሰዎች ፡ አይቀርቡም ፡ ሊማርኳቸ ው ፡ እንጂ ።

በኤርትራ ፡ ዳርና ፡ በትግሬ ፡ ወሰንም ፡ የዲምሆይታና ፡ የዳናኪል ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ አይነታቸው ፡ ይኖራሉ ። ከየግዛታ ቸውም ፡ አያሌ ፡ ከታወቁ ፡ ስፍሮች ፡ እሌህ ፡ ናቸው ።

ምጽዋ ፡ ደሴትና ፡ አገር ፡ የምሥር ፡ ባሻ ፡ ግዛት ። የምጽ ዋ ፡ ሹም ፡ ቃይመቃም ፡ ይባላል ፡ ሹመቱንም ፡ ከጅዳ ፡ መ ኰንን ፡ ይቀበላል ። እርሱም ፡ በዶሆና ፡ አንዲን ፡ ናይብ ፡ የ ሚባለውን ፡ ገዥን ፡ ይሾማል ፡ በሆሆና ፡ በሀዛዎርታ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ። ከሀበሻም ፡ ከሚመጣ ፡ ወዲያም ፡ ከሚገባ ፡ እቃ ፡ ሁሉ ፡ ግብርን ፡ ይወስዳል ።

ዶሆና ፡ (ሀርቂቆ ፡) በምጽዋ ፡ አንጻር ፡ በባሕር ፡ ዳር ። የ ናይብ ፡ መኖርያ ፡ እርሱ ፡ በመካ ፡ ሸሪፍ ፡ ፈንታ ፡ ከምጽ ዋ ፡ ቃይመቃም ፡ በታች ፡ የሆሆን ፡ የሀዛዎርታንም ፡ የዲም ሆይታንም ፡ አሕዛብ ፡ ይገዛል ። እርሳቸውም ፡ በባሕር ፡ ዳ ርና ፡ በትግሬ ፡ መኻከል ፡ ይኖራሉ ። ከዲምሆይታ ፡ ሰዎች ም ፡ በቀር ፡ የአዳሎች ፡ ወይስ ፡ ዳናኪል ፡ ወገን ፡ ናቸው ።

ከምጽዋ ፡ ወደ ፡ ደ ፡ ያለች ፡ የባሕር ፡ ደር ፡ የደናኪል ፡
መኖርያ ፡ ናት ፡ እስከ ፡ ተጉሪ ፡ ጉበት ፡ ድረስ ፡፡ ስፍራው
ም ፡ ስፍራውን ፡ እንደህ ፡ ደከተላል ፡፡ ከገደም ፡ ተራራ ፡
በታች ፡ አንስሌቢ ፡ የምትባል ፡ ጉበት ፡ ከዚያም ፡ የ
ዙላ ፡ መንደር ፡ አለች ፡፡ ከዚያም ፡ በድሮ ፡ ዘመን ፡ አዱ
ላ ፡ የተባለች ፡ ከተማ ፡ ነበረች ፡ ደህና ፡ እብነ ፡ በረደም ፡
ተገኝቶ ፡ ነበር ፡፡ ወደ ፡ ደ ፡ የሁርቱ ፡ ተራራ ፡ ደከተላል ፡፡
ከዚያም ፡ ወደ ፡ ደ ፡ የሀዋኪል ፡ ጉበት ፡ ደከተላል ፡ አያ
ሌ ፡ ታናሾችም ፡ ደሴቶች ፡፡ በደረም ፡ የሀዋኪል ፡ ሰዎች ፡
ደኖራሉ ፡፡ ከዚያም ፡ ወደ ፡ ደ ፡ የሀምፈላ ፡ ጉበት ፡ አለ ፡፡
ሀምፈላና ፡ ቡሬ ፡ ታናሾች ፡ መንደሮች ፡፡ ከዚያ ፡ ደርም ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ተጉሪ ፡ ድረስ ፡ በረሀደታና ፡ በሌሎች ፡ መን
ደሮች ፡ የሚኖሩ ፡ በውድማም ፡ የሚዞሩ ፡ ሰዎች ፡ ደናኪ
ል ፡ ናቸው ፡ እርሳቸውም ፡ አደሎች ፡፡ ለርሳቸውም ፡ ከሸ
ማግሎቻቸው ፡ በቀር ፡ ፬፤ ሥልጣኖች ፡ ወደስ ፡ ደርደሮች ፡
የሚልዋቸው ፡ ገዦች ፡ አልዋቸው ፡ እንደ ፡ በተጉሪ ፡ ከዓ
ድ ፡ ዐሊ ፡ ወገን ፡ አንደም ፡ በአውሳ ፡ ከሙደደቱ ፡ ወገ
ን ፡፡ በማምለካቸውም ፡ እሥላሞች ፡ ናቸው ፡፡

## ፪፪፤ የሾዋ ፡ መንግሥት ፡፡

ደህች ፡ መንግሥት ፡ በቀደም ፡ ከጎንደር ፡ መንግሥት ፡
ጋራ ፡ አንድ ፡ ነበረች ፡፡ ዛሬ ፡ ግን ፡ በሰባተኛ ፡ ትውልድ ፡ ለ
ብቻዋ ፡ ናት ፡፡ ወደ ፡ ምቅ ፡ ወደ ፡ ደ ፡ በሐዋሽ ፡ ወንዝ ፡ ወ
ደ ፡ ሰ ፡ በወሎ ፡ ጋሎችና ፡ በየጁው ፡ ወደ ፡ ምብ ፡ በአባደ ፡
ተወሰነች ፡፡

የምድር ፡ ጠባደ ፡፡ ክሊማ ፡ መኻከለኛ ፡ ነው ፡፡ ምድ
ርም ፡ ደግጥ ፡ በብዙ ፡ ስፍራም ፡ ፍርያም ፡ ናት ፡፡ የቍላን
ና ፡ የደጋን ፡ ፍሬ ፡ ታወጣለች ፡፡ ታላቆች ፡ ወንዞች ፡ አባ
ደ ፡ በምዕራብ ፡ ሀዋሽም ፡ በምሥራቅና ፡ በደቡብ ፡ ናቸ
ው ፡፡ ከርሳቸውም ፡ በቀር ፡ ታናሾች ፡ ወንዞች ፡ መልተዋል ፡፡

ምድር ፡ የምታወጣ ፡ እንደ ፡ በጎንደር ፡ መንግሥት ፡
ነው ፡፡

የጅ ፡ ስራ ፡ መኻየጥም ፡ በቀደም ፡ እንደልነ ፡ ነው ፡፡ የ

ዚኞ ፡ መንግሥት ፡ ንጉሥ ፡ ግን ፡ የስራና ፡ የብልሃት ፡ ወደ
ጅ ፡ ነውና ፡ እንደ ፡ ሰራተኞቹ ፡ እውቀትና ፡ ችሎት ፡ ደህና ፡
ስራ ፡ ያሰራል ፡፡ እንግደ ፡ ሰራተኛም ፡ ቢገባ ፡ የንግደን ፡ ስ
ራና ፡ ብልሃት ፡ ያሰራዋል ፡፡

ባላገሮች ፡፡ ካደነተኞች ፡ ሀበሸኞች ፡ ሌለ ፡ ብዙ ፡ ጋሎ
ች ፡ ደናኪልም ፡ አርጎበኞችም ፡ ናቸው ፡፡ የጉራጌም ፡ ክፍ
ል ፡ ደገበራል ፡፡ አምልኳቸው ፡፡ የክርስቲያን ፡ የሥላሞ
ችም ፡ ያረማውያንም ፡ አምልኮ ፡ አለ ፡፡ የዚኞ ፡ መንግሥ
ት ፡ ክርስቲያን ፡ ሃይማኖታቸውን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡
ቢያቀኑ ፡ የክርስቶስ ፡ ኃይልና ፡ ፍቅርም ፡ በልባቸው ፡ ቢ
መላ ፡ የወንጌል ፡ በርሃን ፡ ከዚህ ፡ በርቶ ፡ በአፍሪቃ ፡ መ
ካከል ፡ በጨለማ ፡ የተቀመጡትን ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉን ፡ ቢ
ያበራ ፡ ወደ ፡ እውነተኛ ፡ አምላክም ፡ ወደ ፡ ተወደደ ፡ ልጁ
ም ፡ ወደ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እውቀት ፡ ቢወስደቸው ፡፡ ደ
ህነንም ፡ ብለው ፡ ወንድሞቻቸው ፡ የንግሊዝ ፡ ቤተ ፡ ክር
ስቲያን ፡ የሚስዮን ፡ ጉባኤዋ ፡ መለክተኞቻቸውን ፡ ላኩ ፡
በወንጌል ፡ አስተምረው ፡ የወንድሞቻቸውን ፡ የሸዋ ፡ ሰ
ዎችን ፡ ልብ ፡ ለሃይማኖትና ፡ ለፍቅር ፡ ያስነሡ ፡ ዘንድ ፡፡
እግዚአብሔር ፡ ደወደልና ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እንዲድን ፡ ሁሉ
ም ፡ ወደ ፡ እውነቱ ፡ እውቀት ፡ እንዲደርስ ፡፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ ልጆችም ፡ ብንሆን ፡ ያባታችን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፍ
ቅር ፡ በልባችንም ፡ ደቃጠላል ፡፡ እርሱንም ፡ ለማያውቁት ፡
እናዝናለን ፡ የርሱም ፡ ፈቃድ ፡ ለሰው ፡ ደህንነት ፡ እንዲ
ፈጸም ፡ እንደክማለን ፡፡ የእግዚአብሔር ፡ ፍቅር ፡ ግን ፡ በ
ልባችን ፡ ባደኖር ፡ ልጆቹ ፡ አይደለነም ፡፡

የመንግሥት ፡ መግዛት ፡፡ የዚኞ ፡ መንግሥት ፡ ንጉ
ሥ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ በታች ፡ ብቻውን ፡ ደገዛል ፡ ኃይሉ
ም ፡ በሕዝቡ ፡ ፈቃድ ፡ አልተወሰነም ፡፡ እርሱም ፡ በመንግ
ሥቱ ፡ ወሰን ፡ አበጋዞች ፡ የሚባሉትን ፡ የወሰን ፡ ጠባቂ
ችን ፡ ሾመ ፡ ቍጥራቸውም ፡ ፶፩፡ ነው ፡፡ ባበጋዞችም ፡ ላ
ይ ፡ ከንጉሥም ፡ በታች ፡ ያበጋዞች ፡ አለቆች ፡ ተሾሙ ፡፡ ካ
በጋዞችም ፡ በቀር ፡ ብዙ ፡ ሌሎች ፡ ገዦች ፡ አሉ ፡፡

የመንግሥት ፡ መክፈል ፡፡ ደህች ፡ መንግሥት ፡ በሁለ

ት ፡ ታላቆች ፡ እኩሌቶች ፡ ትከፈላለች ፡ እርሳቸውም ፡ አ. ፈ.ት ፡ ወደ ፡ ምሥራ.ቅ ፡ ሸዋ ም ፡ ወደ ፡ ምዕራ.ብ ፡፡

አንኮበር ፡ የመንግሥት ፡ ሁሉ ፡ ከተማ ፡ የንጉሥም ፡ መጀመርያ ፡ መኖርያ ፡ ፲፪፲፻፡ ሰዎች ፡፡ የንጉሥ ፡ ቤቶች ፡ በታላቅ ፡ ኮረፍ.ታ ፡ ላይ ፡ ተሠሩ ፡፡ ፳፤ አብያተ ፡ ክርስቲያ ናት ፡፡ የውኃም ፡ ወፍጮ ፡ በአይራ.ራ. ፡ ወንዝ ፡፡

አልዩ ፡ አምባ ፡ የወሰን ፡ ገቢያ ፡፡ ፈ.ሪ ፡፡ ጨኖም ፡፡ አ ደገብርም ፡ መንደሮች ፡ በአደሎች ፡ ወሰን ፡፡ ደችም ፡ ቊ ላ ፡ በሸዋ ፡ ተራ.ሮች ፡ እግር ፡ ያሉ ፡ ከደቡብም ፡ ወደ ፡ ሰ ሜን ፡ የተዘረጋች ፡ ስምዋ ፡ አርጎባ ፡ ነው ፡፡

ደ.ንኪ ፡፡ ቁንደ. ፡፡ በቀደም ፡ ከተማ ፡ ነበረች ፡ እራ.ስ ፡ ወ ሰን ፡ ሰገድ ፡ የሞተባት ፡፡

ደብረ ፡ ብርሃን ፡ የንጉሥ ፡ ሶስተኛ ፡ መኖርያ ፡፡ ገ ቢያ ፡፡

አንጐለላ ፡ አደ.ስ ፡ ከተማ ፡ በጋሎች ፡ ወሰን ፡፡ የንጉሥ ፡ ሁለተኛ ፡ የተወደደውም ፡ መኖርያ ፡፡ የጫጫ ፡ ወንዝም ፡ ይቀርባል ፡፡

ተጉለት ፡ በድሮ ፡ ዘመን ፡ የሀበሻ ፡ ሁሉ ፡ ከተማ ፡ ነበረ ች ፡ ዛሬ ፡ ግን ፡ ታናሽ ፡ መንደር ፡ ናት ፡

ደብረ ፡ ሊበኖስ ፡ ታላቅ ፡ አገር ፡፡ ፫፤ አብያተ ፡ ክርስቲያ ናት ፡ የከበረች ፡ ገደምም ፡፡ አቡና ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ የተወለደበት ፡ ስፍ.ራ. ፡፡ የጤና ፡ ምንጮች ፡፡ ገቢ.ያም ፡፡

ሌሎች ፡ ታላቆች ፡ አገሮችም ፡፡ ዬረር ፡፡ አያምርም ፡ ግ ራ.ምድርም ፡፡ ያሊ.ፋ.ገርም ፡፡ መካነ ፡ ሥላሴም ፡፡

የወሰን ፡ ግዛት ፡ ይህ ፡ ነው ፡፡ እንኮበር ፡ ቦሶም ፡ መንዝ ም ፡ ይቃቂትም ፡ ደብደቦም ፡ ቀራ.ባም ፡ ማጎፏድም ፡ ቃው ትም ፡ አቦምሳም ፡ ግድምም ፡ አንጾኪ.ያም ፡ ኤፍ.ራ.ታም ፡ ጊሼም ፡ ደደርም ፡ ቃያም ፡ ላሎምድርም ፡ ወረሞም ፡ ሚ ደም ፡ ምራ.ቤቴም ፡ ደብብም ፡ ሸዋሜደም ፡ አንጐርጫም ፡ እንጐፌም ፡ ፌቆሜደም ፡ ደ.ደም ፡ ደ.ራ.ም ፡ ጠራ.ም ፡ ደ.ራ.ዞ ም ፡ አሣገርትም ፡፡ ከዚ.ያም ፡ ሌላ ፡ ይህ ፡ አለ ፡፡ ፈ.ጠጋር ፡ ቀምብቢ.ትም ፡ ቡልጋም ፡ ሠጸንም ፡ (ፈ.ንሊ.ን ፡) ደ.ቢ.ም ፡ ጎንሬም ፡ አራ.ምባም ፡ ወደ.ሎም ፡፡

የሸዋ ፡ መንግሥት ፡ ሁሉ ፡ ርዝመት ፡ ከሀዋሽ ፡ እስከ ፡ አባይ ፡ ድረስ ፡ የ፲፫፡ ቀን ፡ መንገድ ፡ ያህላል ፡ (፫፻፡ ሚሌ ፡) ወርድዋም ፡ ከአንጾኪያ ፡ ወደ ፡ ደራ ፡ የ፲፫፡ ቀን ፡ መንገድ ።

---

፫፫። በሀበሻ ፡ ደር ፡ ያለች ፡ ምድር ።

*a.* የአርጎባና ፡ የወሎ ፡ ግዛት ፡ አንደንድ ፡ ጊዜም ፡ ለጎንደር ፡ ንጉሥ ፡ ለራሶ ፡ ግብርን ፡ ትገበራለች ። በሸዋ ፡ ሰሜን ፡ ናት ።

ባላገሮች ፡ አደነተኞች ፡ አርጎባኞችና ፡ ጋሎች ፡ ከወሎ ፡ ከየጁው ፡ ወገን ፡ ናቸው ። አምልኳቸውም ፡ የሥላም ፡ አምልኮ ፡ ነው ።

ዓደናምባ ፡ በጫፈ ፡ ወንዝ ፡ ያርጎባ ፡ ከተማ ። ተሁላደሬ ፡ የየጁው ፡ ከተማ ። የሀይቅ ፡ ባሕር ፡ ከዚያ ፡ አለ ፡ በውሥጡም ፡ በደሴት ፡ ላይ ፡ የቅዱስ ፡ እስጢፋኖስ ፡ ገደም ።

*b.* የጋሎች ፡ ምድር ፡ በሀበሻ ፡ ዙርያ ። የነገደቻቸው ፡ ቍጥር ፡ የምድራቸውም ፡ ስፋት ፡ ገና ፡ አልታወቀም ። የታወቁ ፡ እሌህ ፡ ናቸው ። ደብኣ ፡ አስቦም ፡ በትግሬና ፡ በደናኪል ፡ መኻከል ። ወህላና ፡ ወሎ ፡ የጁውም ፡ በአርጎባኢቱ ፡ አረሲም ፡ ሰርያም ፡ ጭርቅርም ፡ አላም ፡ በደናኪልና ፡ በሶማል ፡ በሀረርም ፡ በሸዋም ፡ መኻከል ። ከርሳቸውም ፡ በቀር ፡ በሸዋ ፡ ሰሜን ፡ እሌህ ፡ አሉ ። ደዌ ፡ ዋራም ፡ ገፍራም ፡ ወቸሌም ፡ ቦተሀም ፡ ሳኮም ፡ ቶራደሬም ፡ ጊሌም ፡ አዘሎም ። በቡልጋም ፡ በኵል ፡ ከሸዋ ፡ በታች ፡ እሌህ ፡ አሉ ። አብጁ ፡ አደደም ፡ ቶደም ፡ አቦም ፡ ሌባንም ፡ ጂታም ፡ አፈሳላም ፡ ጌላንም ፡ ሜታም ። ወደ ፡ ምዕራብም ፡ እሌህ ፡ አሉ ። ሜጫ ፡ ጉድሩም ፡ ብቾም ፡ ቦረናም ፡ አንኮም ፡ ዛድራም ። እሌህም ፡ ወደ ፡ ደ ፡ ኑረው ፡ ይባላሉ ። ሙጋር ፡ አለማሌም ፡ በርጋሞም ፡ ጉማርም ፡ ቡዛሞም ፡ ሶጋሞም ፡ አበደም ፡ ባቢሊደም ። እርሳቸውም ፡ ሁሉ ፡ አንዲት ፡ ሕዝብ ፡ ናቸው ፡ አንድ ፡ ቋንቋም ፡ ይናገራሉ ። አምልኳቸው ። ከርሳቸው ፡ ጥቂት ፡ ተጠመቁ ፡ አ

ያሌም ፡ እሥላሞች ፡ ሆኑ ። ደሩ ፡ ብዛታቸው ፡ ባረሚነት ፡ ይቀመጣሉ ፡ ደምንም ፡ በማፍሰስ ፡ ይመካሉ ። ይህችንም ፡ ሕዝብ ፡ በወንጌል ፡ ማስተማር ፡ ለክርስቲያን ፡ ይገባል ። ወንጌልንም ፡ ቢቀበሉ ፡ ልባቸውን ፡ ከክፉ ፡ ለበጎ ፡ ይለውጣል ። በመግደልም ፡ ፈንታ ፡ መውደድን ፡ ያስተምራቸዋል ፡ ጦርንም ፡ ለማረሻ ፡ ይለውጣል ፡ ሰይፍንም ፡ ለማጭድ ፡ የሰውንም ፡ ባርነትን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ልጅነት ። እግዚአብሔር ፡ ያንን ፡ ዘመን ፡ ቶሎ ፡ ያድርስ ።

c. የሀረር ፡ (አራርጌ ፡) መንግሥት ። ከሸዋ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅና ፡ ወደ ፡ አዜብ ፡ በጋሎችና ፡ በሶማልም ፡ መኻከል ። ከአፍሪቃ ፡ ውሥጥ ፡ ከሚመጡ ፡ ቅፍለቶች ፡ ብዙ ፡ በዚች ፡ ምድር ፡ ያልፋሉ ። ባላገሮች ፡ እሥላሞች ፡ ናቸው ።

ሀረር ፡ ታላቅ ፡ ከተማ ፡ የንጉሥም ፡ መኖርያ ።

d. የሶማል ፡ ሕዝብ ፡ በብዙ ፡ ነገዶች ፡ ተከፈሉ ። ምድራቸውም ፡ ከተጉሪ ፡ ወደ ፡ በርብራ ፡ ወደ ፡ ጓርድፉዊም ፡ ካጽ ፡ ከባሕር ፡ ደርም ፡ ወደ ፡ ሀረር ፡ መንግሥት ፡ ተዘረጋች ። ከነገዶቻቸውም ፡ እሌህ ፡ ፭ ፡ የታወቁ ፡ ናቸው ። ኢሳ ፡ ወራበሬም ፡ ሀርቲም ፡ ጉደቢርሳም ፡ ሀብራወልም ። አምላካቸውም ፡ የሥላም ፡ አምላክ ፡ ነው ። ንጉሥም ፡ የላቸውም ፡ ከየሽማግሎቻቸው ፡ በታች ፡ ናቸው ፡ እንጂ ።

ዘይላ ፡ ታናሽ ፡ ከተማ ፡ በባሕር ፡ ደር ። ገቢያም ፡ መርስም ። ሹሙንም ፡ ከሞኻ ፡ ትቀበላለች ።

በርብራ ፡ የሶማል ፡ ገቢያና ፡ መከማቻ ፡ በባሕር ፡ ደር ። ደህና ፡ መርስ ። የሶማል ፡ ሰዎች ፡ በበጋ ፡ ጊዜ ፡ ተራሮቻቸውን ፡ ትተው ፡ ወደዚህ ፡ ይሰበሰባሉ ፡ የዐረብና ፡ የፈረንጆችም ፡ መርከቦች ፡ መጥተው ፡ ይሸያየጣሉ ። በክረምት ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ሶማሎች ፡ ቤቶቻቸውን ፡ በገመል ፡ ጀርባ ፡ ላይ ፡ ጭነው ፡ ወደ ፡ ተራሮች ፡ ይመለሳሉ ።

e. የጉራጌ ፡ ምድር ፡ ከሸዋ ፡ ወደ ፡ ደቡብ ። ተከፍላ ፡ ለሸዋ ፡ ንጉሥ ፡ ትገበራለች ። ባላገሮች ። በስም ፡ ክርስቲያኖች ፡ እሥላሞችም ፡ አረማውያንም ፡ ናቸው ። የሀዋሽ ፡

ወንዝ ፡ ከዚህ ፡ ይመነጫል ፡፡ ዝዋይ ፡ የሚባል ፡ የምድር ፡ ባሕር ፡ አለ ፡፡ በርሱም ፡ ሞነክሶች ፡ የሚኖሩባት ፡ ደሴት ፡ ትገኛለች ፡፡ ግሥላም ፡ በዚች ፡ ምድር ፡ ይገኛል ፡፡

*f.* የከፋ ፡ ምድር ፡ በጉራጌና ፡ በናርያ ፡ መኻከል ፡፡

*g.* የናርያ ፡ ምድር ፡ ከከፋ ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡፡ ከሁለታቸውም ፡ እጅግ ፡ ቡን ፡ ዝባድም ፡ የግሥላ ፡ ለምድም ፡ ሌላ ፡ እቃም ፡ ይመጣል ፡፡

*h.* ሲደማ ፡ ከናርያ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡፡ በሌህ ፡ ሶስት ፡ ምድሮች ፡ ክርስቲያን ፡ እሥላሞችም ፡ አረማውያንም ፡ ተደባለቁ ፡፡

*i.* የዝንጀሮ ፡ ምድር ፡ ለብቻዋ ፡ ከንጉሥዋም ፡ በታች ፡ ናት ፡ ከጉራጌ ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡፡ ባላገሮች ፡ አረማውያን ፡ ናቸው ፡፡

*j. k.* በከምበትና ፡ በማገር ፡ ምድሮችም ፡ ብዙ ፡ ክርስቲያን ፡ እንደ ፡ ገኙ ፡ ይላሉ ፡፡

---

### 3. የአያን ፡ ምድር ፡፡

ከካጵ ፡ ጓርድፉዊ ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ ወደ ፡ ዛንጅባር ፡ የተዘረጋች ፡ ደርቻ ፡፡ ከዚች ፡ ምድርም ፡ የታወቀ ፡ ነገር ፡ ጥቂት ፡ ነው ፡፡ በውሥጥዋ ፡ ፈርያም ፡ ናት ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ አራዊት ፡ ናቸው ፡ ይባላል ፡፡

---

### 4. ኒግሪትያ ፡ ወይስ ፡ ሱደን ፡፡ የሻንቅሎች ፡ ምድር ፡፡

በአፍሪቃ ፡ ውሥጥ ፡ ትኖራለች ፡ ጥቂትም ፡ ብቻ ፡ ታወቀች ፡፡ በሴኔገምቢያና ፡ በሣሃራ ፡ ምድረ ፡ በደ ፡ በጊኔያም ፡ በጋሎችም ፡ ምድር ፡ በሀበሻም ፡ በኑቢያም ፡ ተወሰነች ፡፡ በመኻከልዋም ፡ ኒገር ፡ (ጥቁር ፡ ወንዝ ፡) ወይስ ፡ ጆልባ ፡ የሚባል ፡ ታላቅ ፡ ወንዝ ፡ ያልፋል ፡፡ እርሱም ፡ ቁራና ፡ ጫደ ፡ ከሚባሉ ፡ ከሁለት ፡ የሚገናኙ ፡ ወንዞች ፡ ላንድ ፡ ታላቅ ፡ ወንዝ ፡ ይሆናል ፡ በጊኔያ ፡ ደርም ፡ ወደ ፡ አትላንቲስ ፡ ወቅያኖስ ፡ ይገባል ፡፡ በዚች ፡ ምድርም ፡ የኮንግና ፡ የጨረቃ ፡ ተራሮች ፡ አሉ ፡፡ የጫድም ፡ ታላቅ ፡ ባሕር ፡

የዛደሬ : ባሕርም :: ክሊማ : እጅግ : ይተኰሳል : ምድር
ም : በብዙ : ስፍራ : ውድማና : መካን : ናት : በኒገር : ደ
ር : ግን : ፍርያም : ናት ::

ምድር : የምታወጣ :: እህል : አያሌም : የመድኃኒ
ት : አታክልት : ጥጥም : እጅግ : እንጨትም :: ፈረስም :
ላምም : ዝሆንም : አንበሳም : ዝንጅሮም : ሰጐንም : ጅ
ራት : ቆጭንም : ቀበሮም : አዞም ::

ባላገሮች :: የሚበዙ : ቫንክሎች : ናቸው : ከርሳቸው
ም : ብዙ : አረማውያን : አያሌ : እሥላሞችም :: ባያ
ሌ : ስፍራቸውም : የተልባግርንና : የጥጥን : ስራ : ይሰራ
ሉ : ሌሎችም : በወርቅ : በመድኃኒትም : በባሮችም : ይሻ
የጣሉ ::

መከፈል :: የታወቁ : መድሮች : እሌህ : ናቸው ::

## ፲፩፤ ቡርኑ ::

ታላቅ : መንግሥት : ናት : ንጉሥ : ያላት :: ለርሱም : የ
ወንገራ : የበገርማም : የሀውሳም : የከሸናም : የደውራ
ም : የካኔያም : የአስብያም : ግዛቶች : ይገበራሉ ::

ቡርኑ : የመንግሥት : ከተማ : የንጉሥም : መኖርያ : በ
ገዛሎች : ወንዝ : ፳፲፱፤ ሰዎች :: አያሌ : መስጊዶች :: የቁ
ማሽም : የጥጥም : የስጋጃም : የማቅም : መስሪዮች :: እ
ጅግ : መሻየጥም : ወደ : ፌስ ::

ገናራ : በወንገራ : ግዛት :: መስራ : በበገርማ : ግዛት ::
ሀውሳ : በሀውሳ : ግዛት :: አጋደስ : ገቢያ : በአስብያ : ግ
ዛት :: ያወር : ከዚያ : በኰል : ሙንጎ : ጳርክ : ሞተ ::

---

## ፲፪፤ ቲምቡክቱ ::

ታላቅ : መንግሥት : ዛሬ : የቫንክላ : ንጉሥ : ወደሚገዛ
ባት :: የብዙ : ቅፍለቶች : መሰብሰቢያ :: ባላገሮች : ተ
ከፍለው : የማውሮች : እሥላሞች : ተከፍላውም : የቫን
ክሎች : አረማውያን : ናቸው ::

ቲምቡክቱ : ከተማ : የንጉሥም : መኖርያ : ፫፻፻፤ ወደ

ስ ፡ ፯፻፻፡ ሰዎች :: ታላቅ ፡ ገቢያ :: ከብሬ ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ፡ በ ኒገር ፡ ደር ::

---

፫፫፡፡ በምበሬ ::

የዚች ፡ መንግሥት ፡ ምድር ፡ ፈርያም ፡ ናት :: እጅግ ፡ ወርቅም ፡ አለባት :: ንጉሥም ፡ ይገዛታል ::

ሴጎ ፡ ከተማና ፡ ገቢያ :: ፵፲፻፡ ሰዎች :: ይኔ ፡ የንጉሥ ፡ መኖርያ ::

የቀሩም ፡ ምድሮች :: ዘሎንጋዴ ፡ መንደንግም ፡ ካርታም ፡ መሲናም ፡ ኮንግም ፡ ከፋባም ፡ ጎቶም ፡ አያሌ ፡ ሌሎችም ፡ ስማቸው ፡ ብቻ ፡ የታወቀ ፡ ነው :: አንዱትም ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ፡ አለች ፡ ወሰና ፡ የሚልዋት ::

---

5. ሴኔገምቢያ ::

ወደ ፡ ሰ ፡ በሣሃራ ፡ ምድረ ፡ በደ ፡ ወደ ፡ ምቅ ፡ በኒግሪትያ ፡ ወደ ፡ ደ ፡ በላይኛ ፡ ጊኔያ ፡ ወደ ፡ ምብ ፡ በአትላንቲስ ፡ ዉቅያኖስ ፡ ተወሰነች :: በምብ ፡ ርዝመት ፡ ፯°፡ — ፲፯°፡ በሰ ፡ ወርድም ፡ ፰°፡ — ፲፯°፡ ትኖራለች :: ክሊማ ፡ ይተኰሳል ፡ ምድርም ፡ ፈርያም ፡ ናት ፡ በምድር ፡ ውሥጥ ፡ እንጅ ፡ ታላቆች ፡ ያሻዋ ፡ ውድሞች ፡ ወደሉ :: አያሌ ፡ ተራሮችም ፡ አሉ :: ካጾች :: ነጭ ፡ ካጽ ፡ ሀረንጊዴ ፡ ካጽም ፡ ቀይ ፡ ካጽም :: ታላቆች ፡ ወንዞች :: ሴኔጋል ፡ በኮንግ ፡ ተራሮች ፡ የሚመነጭ ፡ እርሱም ፡ አያሌ ፡ ደሴቶችን ፡ ያደርጋል :: ደግሞ ፡ ገምቢያ ፡ ከሰምንሶም ፡ ጋሬ ፡ ርዮ ፡ ግረንድም ::

ምድር ፡ የምታወጣ :: ብርብሪ ፡ እጅግ ፡ መድኃኒትም ፡ ሀርም ፡ ጥጥም ፡ ሡክርም ፡ የሺህ ፡ ዛፍም ፡ ተምርም ፡ የቀለም ፡ እንጨትም ፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ ፍሬ ፡ ዛፍም :: ዝሆንም ፡ አንበሳም ፡ ዝንጀሮም ፡ ጉማሬም ፡ የባሕር ፡ ላምም ፡ ብሆርም ፡ ሰጎንም :: ወርቅም ፡ አምብራም ፡ ጨውም ::

ባላገሮች :: የሥላሞችና ፡ ያረማውያን ፡ ሻንክሎች :: ከርሳቸው ፡ ጋራም ፡ ፈረንጆች ፡ ይሸያየጣሉ ::

መክፈል :: በላይኛና ፡ በታችኛ ፡ ሴኔገምቢያ ::

## ፬። ላይኛ፡ ሴኔገምቢያ ።

በሰሜን፡ ናት ። ታላቅ፡ ባለጠግነትዋም፡ ፫፤ የግራር፡ ድ ኖች፡ ናቸው፡ እጅግ፡ ሙጫ፡ የሚወጣባቸው ። እርሳቸ ውም፡ በካዮር፡ ባሕር፡ አጠገብ፡ ይኖራሉ ።

ጶርተንዲክ፡ መርስ ። የንግሊዞች፡ ገቢያና፡ አምባ ።

## ፭። ታችኛ፡ ሴኔገምቢያ ።

በሴኔጋልና፡ በገምቢያ፡ ወንዞች፡ መኻከል ።

*a.* የያሎፎች፡ ግዛት ። እርሳቸው፡ ከየገዦቻቸው፡ በታ ች፡ አሉ ። መልካቸው፡ ከሌሎች፡ ኻንክሎች፡ ያመራል ።

ሂካርኮር፡ ከተማና፡ ገቢያ ።

ሴኔጋል፡ ደሴት፡ የፈራንሲሶች፡ ግዛት ። በርስዋ፡ የል ዊስ፡ አምባ፡ አለች፡ ፫፲፻፤ ሰዎችም ። የጎሬ፡ ደሴት፡ በሴኔጋል፡ ወንዝ፡ ፯፻። ሰዎች ። የቅዱስ፡ ሚካኤል ም፡ አምባ ።

*b.* የፏሌ፡ ግዛት ። እጅግ፡ ፍርያም፡ ከያሌ፡ ገዦችም፡ በታች፡ ናት ።

ጶደርና፡ ቅዱስ፡ ዮሴፍ፡ ደጋላ፡ ፪፤ አገሮች፡ የፈረን ሲሶች፡ ገቢያ፡ ያለባቸው ።

*c.* የመንደንጎች፡ ግዛት ። እርሳቸውም፡ ተከፍለው፡ እሥላሞች፡ ተከፍለውም፡ ክርስቲያን፡ ናቸው ።

ቅዱስ፡ ያዕቆብ፡ የንግሊዞች፡ ደሴት፡ በገምቢያ፡ ወ ንዝ፡ ኩትያር፡ የንግሊዞች፡ ገቢያ ። ካሆንና፡ ከወር፡ ፪፤ አገሮች፡ በሳሉም፡ መንግሥት ። ከኻጭ፡ የጶርቱጊሶ ች፡ ግዛት ። ብርቱ፡ አምባ፡ በቢሳው፡ ደሴት ።

---

## 6. ላይኛ፡ ጊኔያ ።

በኒግሪትያና፡ በጊኔያ፡ ጉበት፡ በመኻከል፡ በሴራ፡ ሌዎ ና፡ ካጶና፡ በሎጴጽ፡ ካጶም፡ በመኻከል ። ደር፡ ሁሉ፡ ሚደና፡ ፍርያም፡ ናት ። የውሥጠኛ፡ ምድርም፡ ደግዋና፡ ድን፡ ናት ። ካጶች ። ሴራ፡ ሌዎና፡ ሮስት፡ ራሶችም፡ ጶ ልማስም፡ ሎጴጽም ። ክሊማ፡ ይተኩሳል ። ሀርመታን፡

የሚባል ፡ ንፋስ ፡ ለጤና ፡ ይጐዳል ፡፡ ወንዞች ፡፡ ሴራ.ሌዎና ፡ ቦልታም ፡ ቨርብሮም ፡ ሚሱራ.ደም ፡ ኢሲኒም ፡ ፎርሞሶም ፡ ቢኒንም ፡ ከለባርም ፡፡

ምድር ፡ የምታወጣ ፡፡ እጅግ ፡ እህል ፡ ሩዝም ፡ አናናስም ፡ ሡክርም ፡ ቡንም ፡ ሙጫም ፡ ኢንዲጎም ፡ ቶምበኮም ፡ ብርብሬም ፡ ዝንጂብርም ፡ ጥጥም ፡ ደህና ፡ እንጨትም ፡፡ ላምም ፡ ዝሆንም ፡ አንበሳም ፡ ሌሎች ፡ አራዊትም ፡ ዝንጅሮም ፡፡ ወርቅም ፡ ሌሎች ፡ ማነራሎችም ፡፡ በመሻየጥ ፡ እጅግ ፡ የሚጠቀሙ ፡ እንግሊዞች ፡ ናቸው ፡ ለባሮች ፡ ደህንነትና ፡ መፈታት ፡ እጅግ ፡ ደክመዋልና ፡ እግዚአብሔር ፡ በረከቱን ፡ አበዛላቸው ፡፡

ባላገሮች ፡፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ አይነት ፡ ሻንክሎች ፡ እርሳቸውም ፡ አረማውያን ፡ እንግሊዞችና ፡ አሜሪካኖች ፡ አርነት ፡ ካወጥዋቸው ፡ ከወንጌል ፡ ምለክተኞችም ፡ የሃይማኖትን ፡ ትምህርት ፡ ከተቀበሉ ፡ በቀር ፡፡ እንግሊዞች ፡ አያሌ ፡ አእላፈን ፡ ከሌህ ፡ ምስኪኖች ፡ ባሮች ፡ ከባርነት ፡ መርከቦች ፡ አድነው ፡ አርነት ፡ አውጥተዋቸዋልና ፡፡ ታላቅ ፡ ግዛትንም ፡ በብር ፡ ገዙላቸው ፡ የተፈቱትንም ፡ የሰውንም ፡ ልጅነት ፡ የተቀበሉትን ፡ ሻንክሎች ፡ ከዚያ ፡ አስቀመጡ ፡፡ ለበስዋቸውም ፡ ስራውንም ፡ ሃይማኖትንም ፡ ትምህርትንም ፡ አስተማርዋቸው ፡፡ ዛሬም ፡ እሌህ ፡ ሻንክሎች ፡ አያሌን ፡ ደህኖች ፡ ከተሞችንና ፡ መንደሮችን ፡ ሠሩ ፡ በደህና ፡ ትምህርትም ፡ ተቀምጠው ፡ ያድጋሉ ፡፡ ባሜሪካ ፡ ደግሞ ፡ አያሌ ፡ ጉባኤዎች ፡ የንግሊዞችን ፡ ፍለጋ ፡ ተከትለው ፡ በሊቤርያና ፡ በጳልማስ ፡ ካጵ ፡ ሁለትን ፡ የሻንክሎችን ፡ ኮሎኒዮች ፡ ሠሩ ፡፡

መከፈል ፡፡

## ፩፩። የሴራ ፡ ሌዎና ፡ ደር ፡፡

ከሴራ ፡ ሌዎና ፡ ካጵ ፡ ከኑኔጽ ፡ ወንዝም ፡ እስከ ፡ ቅድስት ፡ አና ፡ ካጵ ፡ ድረስ ፡፡ በርስዋም ፡ የሴራ ፡ ሌዎና ፡ ኮሎኒያ ፡ የቲማኖችም ፡ የፉላም ፡ የሱሱም ፡ የባጎም ፡ ግዛቶች ፡ አሉ ፡ ከብዙ ፡ ደሴቶች ፡ ጋራ ፡፡ ደግሞም ፡ የቡሎም ፡

ግዛት ፡ በርሳቸው ፡ መኻከል ፡ የወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ ያስተማሩ ፡ መጽሐፍ ፡ ቅዱስንም ፡ በቋንቋቸው ፡ አስተረጐሙ ።

– ፍሪተውን ፡ የሴራ ፡ ሌዎና ፡ ከተማ ፡ የመስለኒም ፡ መኖርያ ። አያሌ ፡ ከወንጌል ፡ መለክተኞች ። አያሌ ፡ ማስተማርዮች ።

ሌስተር ፡ ፪፻፪፤ ሰዎች ፡ አያሌ ፡ ማስተማርዮችና ፡ መስራዮች ። በሌስተርም ፡ ተራራ ፡ ሴሚናር ፡ አለች ፡ የሻንክሎት ፡ ተማሮች ፡ መምህራን ፡ ለመሆን ፡ ወደሚማሩባት ።

ሪጀንትስተውን ፡ ደህና ፡ ከተማ ። አያሌ ፡ ማስተማርዮችና ፡ መሰራዮች ። ዋተርሎ ፡ ማስተማርያ ። ከንት ። ኪሴም ።

የበሀማ ፡ ደሴቶች ። የወንጌል ፡ መለክተኛ ። አያሌ ፡ ማስተማርዮች ።

---

## ፪፪፡፡ የብርብሪ ፡ ደር ።

ከቅድስት ፡ አና ፡ ካጵ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ጰልማስ ፡ ካጵ ፡ ድረስ ። በዚችም ፡ ደር ፡ አሜሪካኖች ፡ አንደኛ ፡ ደህና ፡ ኮሎኒያን ፡ አርነት ፡ ለወጡ ፡ ባሮች ፡ በሜሱራደ ፡ ካጵ ፡ አጠገብ ፡ ሠሩ ፡ ሊቤርያም ፡ ብለው ፡ ጸርዋት ። አያሌንም ፡ መምህራን ፡ ከወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ ሰጡላቸው ። በጰልማስ ፡ ካጵም ፡ ሁለተኛውን ፡ ኮሎኒያን ጀመሩ ።

በባሲልም ፡ ያለች ፡ የሚስዮን ፡ ጉባኤ ፡ አያሌን ፡ ከወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ ወደ ፡ ሊቤርያ ፡ ሰደደ ፡ በአሸንቲ ፡ ሕዝብ ፡ መኻከል ፡ ወንጌልን ፡ ለማስተማር ። አያሌ ፡ ግን ፡ ሲሞቱ ፡ የቀረም ፡ እጅግ ፡ ሲቸገሩ ፡ ተውት ። እንደሁም ፡ የንግሊዞች ፡ የአሜሪካኖችም ፡ የንምሳም ፡ ክርስቲያን ፡ ያንድ ፡ ልብ ፡ ሆኑ ፡ እልያን ፡ ሻንክሎችን ፡ በሰደጣን ፡ ስራ ፡ ለባርነት ፡ የተኰነኑትን ፡ ወደ ፡ ሰው ፡ ልጅነት ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልጅነት ፡ እንጅ ፡ ይወስድዋቸው ፡ ዘንድ ። በዚህም ፡ ስራ ፡ እጅግ ፡ ድካምን ፡ አገኙ ፡ እጅግ ፡ ሞትንም ፡ ያገርንም ፡ ድካም ፡ የባሮች ፡ ተ

ቫያሌችንም ፡ ጸላትነት ፡ የቫንክሎችንም ፡ ስንፍና ፡፡ እር ሳቸው ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡ በሃይማኖት ፡ አልደከ ሙም ፡፡ እግዚአብሔርም ፡ በነፍስና ፡ በሥጋ ፡ ባረካቸው ፡፡ ዛሬም ፡ የስራቸውን ፡ ፍሬ ፡ ያያሉ ፡፡ ብዙ ፡ ቫንክሎች ፡ በ ቀደም ፡ ከንስሮች ፡ በታች ፡ ሁነው ፡ የተቍጠሩ ፡ ከሰይጣን ፡ ጨለማ ፡ ወደ ፡ ወንጌል ፡ ብርሃን ፡ ደረሱ ፡ በሥጋዊትና ፡ በ መንፈሳዊትም ፡ ብልሃት ፡ በውቀትም ፡ በደህንነትም ፡ ከ ፈርንጆች ፡ ጋራ ፡ ትክክል ፡ ሆኑ ፡፡ የእንግሊዝ ፡ ገቢያም ፡ እጅግ ፡ ተጠቀመ ፡፡ በቀደም ፡ ከዚያ ፡ ጥቂት ፡ እቃ ፡ ብቻ ፡ ከ ተሻየጡ ፡ ዛሬ ፡ የባርነትን ፡ ገቢያ ፡ ከከለከሉ ፡ ወዲህ ፡ እጅ ግ ፡ በመሻየጥ ፡ ያተርፋሉ ፡፡

---

## ፫፫፡፡ የዝሆን ፡ ጥርስ ፡ ደር ፡፡

ከጸልማስ ፡ ካጽ ፡ ወደ ፡ አጶሎኒያ ፡ ካጽ ፡ ተዘረጋች ፡፡

---

## ፬፬፡፡ የወርቅ ፡ ደር ፡፡

በዚች ፡ ደር ፡ የአሸንቲ ፡ መንግሥት ፡ የሳኩም ፡ የአክሲ ምም ፡ የአኳጺምም ፡ የፌቱም ፡ የፋንቲም ፡ የአጉናም ፡ የሀንታም ፡ የአጶሎኒያም ፡ ሌሎችም ፡ ግዛቶች ፡፡

አሸንቲ ፡ ያሸንቲ ፡ መንግሥት ፡ ከተማ ፡፡ ፌቱ ፡ ታላቅ ፡ አገር ፡ በፌቱ ፡ ግዛት ፡፡ ታላቅ ፡ ኮርመንቲ ፡ በዛንቲ ፡ ምድር ፡፡

### የፈርንጆች ፡ ግዛት ፡ በዚች ፡ ደር ፡፡

A. የንግሊዞች ፡ ግዛት ፡፡ ካጽ ፡ ኮርሶ ፡ ብርቱ ፡ አገ ር ፡፡ የገዢም ፡ መኖርያ ፡፡ ደህና ፡ ገቢያም ፡፡ ካጽኮስት ፡ ካስትል ፡ ብርቱ ፡ አምባ ፡፡ አንማለዉ ፡፡ አክራም ፡፡ ዊ ምባም ፡፡ ኮመንደም ፡ ሌሎችም ፡ ብርቶች ፡ ቦቶች ፡፡

B. የሆላንዲሶች ፡ ግዛት ፡፡ እልሚና ፡፡ ፍሪድሪኽ ስቡርግም ፡፡ ነሳውም ፡ ሌሎች ፡ አገሮችም ፡፡

C. የፈረንሲሶች ፡ ግዛት ፡፡ ፍራንስዋ ፡ አምባ ፡፡ ፪፡ ደሴቶችም ፡ በቤኒን ፡ ወንዝ ፡ አፍ ፡፡

D. የደኖችም ፡ ግዛት ፡፡ ክርስቲያንስቡርግ ፡፡ የአ ኳጺም ፡ ተራሮች ፡ ቅርብ ፡ ናቸው ፡ የሚስዮን ፡ ስፍራ ፡ ወ ደለ ፡፡ ፍሪደንስቡርግ ፡፡ ጵሪንጵንስተደን ፡፡ ኬኒግስተ ደን ፡ ሌሎች ፡ ቦቶችም ፡፡

E. የጶርቱጊሶች ፡ ግዛት ፡፡ የግሌጊ ፡ አምባ ፡፡

---

## ፷፷፡ የባሮች ፡ ደር ፡፡

በዚች ፡ ደር ፡ የባሮች ፡ ገቢያ ፡ ገና ፡ አልተሻረም ፡፡ ኤሌ ህ ፡ ግዛቶችም ፡ አሉ ፡፡ ጎንሰልቦ ፡፡ ደሆሜም ፡፡ ፊደም ፡ ለፍርንጀች ፡ አያሌ ፡ ግዛት ፡ ወደለበት ፡፡ ቤኒንም ፡ ታላ ቅ ፡ መንግሥት ፡፡ ከለባርም ፡፡ አዮም ፡ ከልቦንጎም ፡ የሌሎችም ፡ አሕዛብ ፡ ግዛት ፡፡

አሆሜይ ፡ ፳፻፲፱፡ ሰዎች ፡ በደሆሚ ፡ መንግሥት ፡፡ ከል ሚና ፡ ፲፻፲፱፡ ሰዎች ፡፡ ግሪቢ ፡ ፳፲፱፡ ሰዎች ፡፡ የከበረ ፡ ደን ጊያ ፡ መስሪያ ፡፡ ሳዊ ፡ የባብ ፡ መቅደስ ፡ ወደለበት ፡፡ ቤኒ ን ፡፡ አሬቦ ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ፡ ለፍርንጀች ፡፡ ከለባር ፡ የባሮ ች ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ፡፡

---

## 7. በአትለንቲስ ፡ ዉቅያኖስ ፡ ያሉ ፡ የመኻከለኛ ፡ አፍሪቃ ፡ ደሴቶች ፡፡

### ፩፩፡ የጶርቱጊሶች ፡ የሀረንጊዴ ፡ ካጵ ፡ ደሴቶች ፡፡

እርሳቸውም ፡ ፲፡ ናቸው ፡ እርሳቸውም ፡ ታናሾች ፡፡ ክሊ ማ ፡ ለጤና ፡ ክፉ ፡ ነው ፡ እጅግ ፡ ይተኩሳልም ፡፡ ምድር ፡ የምታወጣው ፡፡ ወደን ፡ ሡክርም ፡ ጥጥም ፡ ኦርስለይ ም ፡ ጭውም ፡ ፍየልም ፡ በግም ፡ ዖፍም ፡ ዓሣም ፡፡ ባላገ ሮች ፡፡ ፩፱፱፡ ሰዎች ፡፡ እርሳቸውም ፡ ጥቂት ፡ ፍርንጆች ፡፡ ሙላቶችም ፡፡ ሻንክሎችም ፡፡ አምልኳቸውም ፡ የሮምያ ፡ መንገድ ፡ ነው ፡፡ እርሳቸውም ፡ ዝንጉርን ፡ ልብስ ፡ ይሰሪ ሉ ፡ በቍርበትም ፡ በጭውም ፡ በቅቤም ፡ በከብትም ፡ ከመ ርከበኞች ፡ ጋራ ፡ ይሻየጣሉ ፡፡

*a.* ሰንያጎ : ደሴት ። ጶርቱ : ጶሪያ : መርሰና : ከተማ : ፺፲፱ ሰዎች ።

*b.* ሰኒኮሉ ። ፯፲፱ ሰዎች ።

*c.* ደልፈዊን : ታላቅ : ተራራ : ነው : ቀድሞም : ቡልካና : ነበረ ።

የቀረ.ም : አሌህ : ናቸው ። ብራዋ : ማዮም ። ደልሰሌም ። ቦናቢስታም : ሰንቱንዮም : ሰንቢንቸንትም : ሰንታሉኪያም ።

## ፪፪። የጊኔያ : ደሴቶች ።

### *a.* የስጳንያ : ደሴቶች ።

ፈርናንደ ጶ : ፲፭፻፡ ሰዎች ። የገዢ : ደሴት ።

### *b.* የጶርቱጊሶች : ደሴቶች ።

ሰንቶማስ : ፲፭፲፱፡ ሰዎች ። እጅግ : ፈርያም : ናት ።

ሰንቶማስ : ከተማ : የገዢና : የኤጲስቆጶስ : መኖርያ ። ፬፡ አብያተ : ክርስቲያናት ። ገደምም ። ሰን : ሴባስትያን : አምባ ። ብዙ : መስሪዮች ።

## ፫። የደቡብ : አፍሪቃ ።

### 1. ታችኛ : ጊኔያ ።

ከሎጴጵ : ካጵ : ጀምሬ : እስከ : ኔግሮ : ካጵ : ድረስ : ተዘረጋች ። ክሊማ : ምድርም : የምድር : ፈሬም : እንደ : በላይኛ : ጊኔያ : ናቸው ። ታላቅ : ወንዝም : ዛይሬ : ወይስ : ኮንጎ ። ባላገሮች : ሻንክሎች : ናቸው ። እርሳቸውም : ተከፍለው : በስም : ክርስቲያን : ተከፍለውም : አረማውያን : ናቸው ። በዚች : ምድርም : ለጶርቱጊሶች : እጅግ : ግዛትና : ገቢያ : አላቸው ። የሚሸዮጥም : ይህ : ነው ። ዝንጅሮ : ዶፍም : የዝሆን : ጥርስም : ባሮችም : እንጨትም ።

፩፩። ልዋንጎ ። ልዋንጎ : ወይስ : ባሊ : ከተማ ። የጣዖት : መቅደስ ።

፪፪። ከጎንጎ ። ኪንጌላ ፡ የንጉሥ ፡ መኖርያ ። መሊ ምባ ፡ መርስ ። የፈረንጆች ፡ ገቢያ ።

፫፫። አንጎዮ ። ከልዋንጎ ፡ በታች ፡ ናት ። ከዚህ ፡ ጥቁ ር ፡ አይሁድና ፡ ቀይ ፡ ሻንክሎች ፡ አሉ ፡ ይላሉ ። ከቢንዴ ፡ የባሮች ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ።

፬፬። ኮንጎ ። ተራሮች ፡ እጅግ ፡ ሜታሎችን ፡ ያወጣሉ ።

ኮንጎም ፡ በሌህ ፡ ግዛቶች ፡ ተከፈለች ። ጶምባ ። ሶኒም ። በምባም ። አዋንደም ። በታም ። ሱንዲም ። ለጶርቱጊሶ ችም ፡ እሌህ ፡ አገሮች ፡ አሉ ።

ሰን ፡ ሰልባደር ፡ የገዢና ፡ የኤጲስቆጶስ ፡ መኖርያ ፡ ፬፻፪፤ ሰዎች ። አያሌ ፡ አብያት ፡ ክርስቲያናትና ፡ ገደሞች ።

ጶምባ ፡ ፪፻፤ ሰዎች ። የሻንክሎችና ፡ የጶርቱጊሶች ፡ ገ ዢ ፡ መኖርያ ።

፭፭። አንጎላ ። ለጶርቱጊሶች ፡ ትገበራለች ። የሻንክሎ ችም ፡ ንጉሥ ፡ የሮምያ ፡ ወገን ፡ ክርስቲያን ፡ ነው ። ደህ ች ፡ ምድርም ፡ ሚነራሎች ፡ ዝሆንም ፡ ዝንጅሮም ፡ መልተ ውባታል ። ደልዋንደ ፡ ፭፲፪፤ ሰዎች ። የጶርቱጊሶች ፡ ሹ ምና ፡ የኤጲስቆጶስ ፡ መቀመጫ ፡ ገቢያም ፡ ለባሮች ፡ ለዝ ሆን ፡ ጥርስም ፡ ለወርቅም ።

፮፮። መተምባ ። የጀጎች ፡ ምድር ፡ ጋሎችን ፡ የሚ መስሉ ።

፯፯። በንጌላ ። የጉበር ፡ ወንዝ ፡ ደችን ፡ ምድር ፡ በ፪፤ ክፍል ፡ ይከፍላል ። የሰሜንም ፡ እኩሌታ ፡ ለጶርቱጊሶ ች ፡ ትገበራለች ። ቅዱስ ፡ ፊልጶስ ፡ ፪፻፤ ሰዎች ፡ የጶርቱጊ ሶች ፡ ሹም ፡ መኖርያ ። አምባ ። የሻንክላ ፡ ንጉሥም ፡ መኖርያ ።

---

## 2. የውሥጥ ፡ ምድር ።

የኮንግ ፡ ተራሮች ፡ በምዕራብ ፡ የሉጶታም ፡ ተራሮች ፡ በ ምሥራቅ ፡ አሉ ። የዘምቢዜም ፡ የዛይሬም ፡ የኳዋንዛ ም ፡ ወንዞች ፡ ከዚያ ፡ ይመነጫሉ ። የመራዊም ፡ ታላቅ ፡ ባሕር ፡ በውሥጥ ፡ አለ ። ተኩሳትዋ ፡ ታላቅ ፡ ናት ። ምድ

ርም ፡ ጥቂት ፡ ፍሬን ፡ ታወጣለች ። እሌህ ፡ አሕዛብ ፡ ደኖ
ረባታል ። የጀጋ ፡ ሕዝብ ፡ በምዕራብ ። ጋሎችም ፡ በሰሜ
ን ። ቀፍሮችም ፡ በደቡብ ። እርሳቸውም ፡ ሁላቸው ፡ አረ
ማውያን ፡ ናቸው ።

---

### 3. የምሥራቅ ፡ ደር ።

፩፩። የዘንጀባር ፡ ወደስ ፡ ዘንግባር ፡ ምድር ፡ካያን ፡ ደር ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ደልጋደ ፡ ካጵ ፡ ድረስ ።

*a.* የመገደክሶ ፡ መንግሥት ፡ ተከፍላ ፡ለጶርቱጊሶች ፡ ትገበሬለች ። እጅግ ፡ ረዝ ፡ ሌላ ፡ እህልም ፡ ላምም ፡ ዝሆንም ፡ አሉባት ።

*b.* የመሊንደ ፡ መንግሥት ፡ ተከፍላ ፡ ለመስከት ፡ ኢማም ፡ የምትገበር ።

*c.* የመረከቶችና ፡ የመከደች ፡ ምድር ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ።

*d.* የዩባ ፡ ምድር ፡ እጅግ ፡ ወርቅና ፡ አምብሬ ፡ ወደለባት ።

*e.* የብሬዋ ፡ሬጱብሊካ ።

*f.* የኰልዋ ፡ መንግሥት ።

መገደክሶ ፡ የመገደክሶ ፡ ከተማ ፡ የንጉሥም ፡ መኖርያ ። መርስ ።

መሊንደ ፡ የመሊንደ ፡ መንግሥት ፡ ደህና ፡ ገቢያና ፡ መርስ ።

ማምገዛ ፡ የመስከት ፡ ግዛት ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ፡ በወርቅ ፡ በዝሆን ፡ ጥርስም ፡ በሰምዕም ። ከዚያም ፡ ፫፧ የኮብሬ ፡ ደሴቶች ፡ ደቀርባሉ ፡ እርሳቸውም ፡ ጶምባ ፡ ዛንዝባርም ፡ መንፊያም ።

፪፪። ሞዘምቢክ ። ከደልጋደ ፡ ካጵ ፡ ጀምሬ ፡ እስከ ፡ ኳም ፡ ወንዝ ፡ ድረስ ። ከመንጋሎ ፡ መንግሥትም ፡ ከመኳ ፡ ዚምባም ፡ ከቦሮሮም ፡ ምድር ፡ ጋሬ ። በምሥራቅዋም ፡ የሞዘምቢክ ፡ ደሴት ፡ አለች ፡ የጶርቱጊሶች ፡ ግዛት ።

ሞዘምቢክ ፡ ከተማ ፡ ፪፲፱፡ ሰዎች ፡ ከባርች ፡ ሌለ ። የ ጶርቱጋል ፡ መስለኒ ፡ መቀመጫ ፡ ታላቅ ፡ ገቢያም ።

---

4. ያፍሪቃ ፡ ደቡብ ፡ ጫሬቨ ፡ የቀፍሮችና ፡ የካጵ ፡ ምድር ።

ክሊማ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ነው ፡ ደረ ፡ በብዙ ፡ ስፍራ ፡ ይተኰሳ ል ። ምድርም ፡ ደግጥ ፡ ናት ፡ ብዙ ፡ ውድማና ፡ ደንም ፡ አ ለባት ፡ በብዙ ፡ ስፍራ ፡ ግን ፡ ፍርያም ፡ ናት ። ተራሮች ። ሉጶታ ፡ ፏሬም ፡ የውርጫም ፡ ተራሮች ። ወንዞች ። ዘም ቤዜ ፡ ከነኒም ፡ ያሣ ፡ ወንዝም ፡ የዝሆን ፡ ወንዝም ፡ ሎረ ንጽም ፡ ቱምቦም ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ወንዝም ። ምድር ፡ የምታወጣ ። ሩዝ ፡ ስንዴም ፡ ያታክልት ፡ ፍሬም ፡ እጅ ግ ። ልዩ ፡ ልዩ ፡ ከብትም ፡ አራዊትም ፡ እንደ ፡ ዝሆን ፡ አ ንበሳም ፡ ነምርም ፡ ተኵላም ፡ ቀበሮም ። ወርቅም ፡ ነሓስ ም ፡ ብርም ፡ ብረትም ፡ ሌሎች ፡ ሚነራሎችም ።

፩፩፡፡ የምዕራብ ፡ ምድር ። የናመኳ ፡ መንግሥት ፡ የ ኦረኝ ፡ ወንዝ ፡ የሚያልፍባት ። ከዚህም ፡ የሚሰዮን ፡ ስራ ፡ ይደረጋል ፡ በሌህ ፡ ቦቶች ። ጸላ ። ቤትስደም ። ቢታን ያም ። ከናመኳ ፡ ሰዎችም ፡ ብዙ ፡ ወደ ፡ ክርስቶስ ፡ አው ቀት ፡ ደረሱ ፡ በወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ ትምህርት ።

፪፪፡፡ የውሥጥ ፡ ምድር ፡ አርሰዋም ፡ የቢችዋና ፡ የቺ ኮዋም ፡ የቡትናም ፡ የኮረናም ፡ የሰሚን ፡ ሆተንቶቶችም ፡ ግዛት ። ከዚያም ፡ ብዙ ፡ ከወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ ያስተ ምራሉ ። አሕዛብም ፡ እጅግ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይናፈቃሉ ። የታወቁም ፡ ስፍሮች ፡ እሌህ ፡ ናቸው ።

ለተኩ ፡ የቢችዋኖች ፡ መጀመርያ ፡ ስፍራ ። የወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ ወደሉ ። ረምጶምጲም ፡ አደስ ፡ አገር ። ዜ ኔብራ ፡ በቡትና ፡ ምድር ። ግሪኳ ፡ በኮረና ፡ ምድር ፡ የወን ጌል ፡ መለክተኞች ፡ ስፍራ ፡ ፯፸፱፡ ሰዎች ። ሊሊፈውንቴ ን ፡ የሚሰዮን ፡ ስፍራ ።

፫፫፡፡ የምሥራቅ ፡ ደር ። የቀፍሮች ፡ ምድር ።

ሀ. የቦሬላና ፡ የቤና ፡ ደር ፡ ኣስክ ፡ ታላቅ ፡ ኣስክ ፡ ሣ

ሣ ፡ ወንዝ ፡ ድረስ ። ከዚያም ፡ እሌህ ፡ መንግሥቶች ፡ አሉ ። ሞኖሞተጳ ፡ ማከረንጋም ፡ ሳቢያም ፡ ሶፈላም ፡ መኒካም ፡ ቢሪም ፡ ኢንሀምበኤም ።

ሲምባዌ ፡ የሞኖሞተጳ ፡ ከተማ ። መሰጴደ ፡ የወርቅ ፡ ገቢያ ። ሰናና ፡ ሶፈላ ፡ የጶርቱጊሶች ፡ ግዛት ።

*b.* የላግዌ ፡ ደር ፡ ከማርያምና ፡ ከዝሆን ፡ ደሴቶች ፡ ጋራ ።

*c.* የናታል ፡ ምድር ፡ ባሣ ፡ ወንዝና ፡ በዞም ፡ ወንዝ ፡ መኻከል ፡ ከመኮሶችና ፡ ከተምቡኮችም ፡ ከመምቡኮችም ፡ ምድሮች ፡ ጋራ ። ከዚያም ፡ እጅግ ፡ ነሣስ ፡ ይወጣል ።

፱፱። የሆትንቶቶች ፡ ምድር ፡ አርስዋም ፡ የካጵ ፡ ኮሎኒያ ። የእንግሊዞች ፡ ግዛት ።

ክሊማ ፡ በጨደ ፡ ተኵስ ፡ ነው ፡ ደረ ፡ ንፋሳት ፡ ጥቂት ፡ ያበርዷታል ። አያሌ ፡ ምድርም ፡ በረኻ ፡ ናት ፡ የቀረችም ፡ እጅግ ፡ ፍሬን ፡ ታወጣለች ። በከረ ፡ ምድረ ፡ በደ ፡ እጅግ ፡ ብረት ፡ ይገኛል ። ተራሮች ። ታፌልበርግ ፡ የሰይጣንም ፡ ተራራ ፡ ያንበሳም ፡ ተራራ ። ካጶች ። የበጎ ፡ ተስፋ ፡ ካጵ ፡ የተሳሳተ ፡ ካጵም ፡ የመርፌ ፡ ካጵም ። ጉበቶች ። የታፌል ፡ ጉበት ፡ የተሳሳተች ፡ ጉበትም ፡ የሰልደንሃ ፡ ጉበትም ፡ የሄሌና ፡ ጉበትም ። ምድር ፡ የምታወጣው ። እህል ፡ የዛፍ ፡ ፍሬም ፡ ደህና ፡ ወይንም ፡ ማርም ፡ ቡንም ፡ ጥጥም ፡ ከምፍርም ፡ ዘይትም ። ላምም ፡ በግም ፡ ፍየልም ፡ በግም ፡ ጎሽም ፡ ዝሆንም ፡ አንበሳም ፡ ሌሎችም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ አራዊት ።

ባላገሮች ። ሆትንቶቶች ፡ ቡሽማኖችም ፡ ቀፍሮችም ፡ ሆንክሎችም ፡ ፈረንጆችም ። አምልኳቸው ። ዛሬ ፡ በወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ በትምህርታቸው ፡ በሁሉ ፡ ዘንድ ፡ የክርስቲያን ፡ አምልኮ ፡ ተዘረጋ ፡ ጥቂት ፡ አረማውያን ፡ ቀርተው ። ብዙ ፡ የወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ ከልዩ ፡ ልዩ ፡ ጉባኤ ፡ ተልከው ፡ በዚች ፡ ምድር ፡ ያስተምራሉ ። ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተመለሱ ፡ በክርስቶስ ፡ ሃይማኖትም ፡ ደኑ ። የሚያምኑም ፡ አካሔዳቸው ፡ ሃይማኖታ

ቸውን ፡ ያስጌጻል ። እርሳቸው ፡ ደህናን ፡ ስራውን ፡ ሁሉ
ን ፡ ተምረው ፡ ይሰራሉ ።

መግዛት ። የንግሊዝ ፡ ንግሥት ፡ መስለኒ ፡ ከሸንጎ ፡ ጋ
ራ ፡ እንደ ፡ እንግሊዝ ፡ ሕግ ፡ ይገዛል ።

ኬጵተውን ፡ ከተማ ፡ ፻፲፱፡ ሰዎች ። የመስለኒ ፡ መኖር
ያ ። አምባ ። ደህና ፡ መርስም ፡ የመርከብም ፡ መስሪያ ።
አያሌ ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናትም ፡ ብዙ ፡ ማስተማርዮ
ችም ፡ አያሌም ፡ ከወንጌል ፡ መለክተኞች ። የሚስዮን
ና ፡ የመጽሐፈ ፡ ቅዱስ ፡ ጉባኤዮችም ፡ እጅግ ፡ መሸየጥ
ም ። ኮንስታንቲያ ፡ እጅግ ፡ ደህና ፡ ወይን ፡ ወደለ ።
የሮቦች ፡ ደሴት ፡ በታፍል ፡ ጉበት ። ስተለንቦሽ ፡ ፲፱፡ ሰ
ዎች ፡ የሚስዮን ፡ ስፍራ ። ባዊያንስክሉፍ ። ግናደን
ታልም ። ግሪንክሉፍም ፡ የወንጌል ፡ ወንድሞች ፡ ስፍ
ራ ። ቤተልስደርፍ ፡ ኤኖንም ፡ ቱልበኽም ፡ ግራፍረይ
ነትም ፡ ቡጶርታልም ፡ ግሬሀምስተውንም ፡ ኤበን ፡
ዔዘርም ። በሌህ ፡ ቦቶች ፡ ሁሉ ፡ ባያሌ ፡ ሌሎችም ፡ የወ
ንጌል ፡ መለክተኞች ፡ ያስተምራሉ ፡ እጅግ ፡ አረማውያን
ም ፡ በውነት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተመለሱ ።

ፍሬድሪክስቡርግ ፡ አምባ ። ግሪኳተውን ፡ የሚስ
ዮን ፡ ስፍራ ። ጆርጅተውን ፡ ያመረች ፡ ቦታ ።

---

## 5. የደቡብ ፡ አፍሪቃ ፡ ደሴቶች ።

### ፩፩፡ በህንድ ፡ ውቅያኖስ ።

A. የሲሸሎች ፡ ደሴቶች ፡ ፻፬፡ ናቸው ፡ የንግሊዞች ፡
ግዛት ።

B. የአሙረንቶች ፡ ደሴቶች ፡ የጶርቱጊሶች ፡ ግዛት ።

C. የኮሞሮች ፡ ደሴቶች ፡ ፬፡ እጅግ ፡ ከብትና ፡ እህል ፡
አለባቸው ። ባላገሮች ፡ እሥላሞችና ፡ ሻንክሎች ፡ ናቸው ፡
ላንድ ፡ ሥልጣን ፡ የተገዙ ፡ መኖርያው ፡ በመሸዲ ፡ ያለ ።

D. መደገስካር ፡ ታላቅ ፡ ደሴት ፡ ስፋትዋ ፡ ፲፯፻፻፡ ማ
ላ ፡ ያለች ። አያሌ ፡ ተራሮች ፡ አሉባት ። ምድርም ፡ እጅ

ግ ፡ ፍሬን ፡ ታወጣለች ፡፡ ባላገሮች ፡ ፬፡ ወይስ ፡ ፫፡ ሚሊዮን ፡ ያህል ፡ ይሆናሉ ፡፡ እርሳቸውም ፡ አረማውያን ፡ ናቸው ፡፡ የወንጌል ፡ መለክተኞችም ፡ በዚች ፡ ደሴት ፡ አስተማሩ ፡ ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ የክርስቶስን ፡ ሃይማኖት ፡ ተቀበሉ ፡፡ ደረ ፡ ንጉሥ ፡ በሞተ ፡ ጊዜ ፡ ምሽቱ ፡ አወጣቻቸው ፡ ክርስቲያንንም ፡ አሳደደች ፡፡ ዛሬም ፡ ብዙ ፡ ክርስቲያን ፡ ከዚያ ፡ አሉ ፡ በስደታቸው ፡ ሁሉ ፡ በሃይማኖት ፡ የሚጸኑ ፡፡ ጾምበቶክና ፡ ተነናሪብ ፡ ከተሞች ፡፡

E. መስከሬኖች ፡፡

*a.* ቡርቦን ፡ የፈራንሲሶች ፡ ግዛት ፡፡ ክሊማ ፡ ደህና ፡ ነው ፡፡ አንድ ፡ የሚቃጠል ፡ ቡልካኖ ፡ አለ ፡፡ ምድር ፡ እጅግ ፡ ፍርያም ፡ ናት ፡ እጅግ ፡ መሻየጥም ፡ አለ ፡፡ ሰዎች ፡ ከ፲፻፡ ይበዛሉ ፡ እርሳቸውም ፡ ፈረንሲሶች ፡ ክሬዎሎችም ፡ ሻንክሎችም ፡፡ ሰንት ፡ ዴኒስና ፡ ሰንት ፡ ጳውሎስ ፡ ከተሞች ፡፡

*b.* መውሪትዩስ ፡ የንግሊዞች ፡ ግዛት ፡ ፳፻፡ ሰዎች ፡ ከርሳቸውም ፡ ፳፭፲፻፡ ፈርንጆች ፡፡ ቡልካኖችም ፡ አሉባት ፡፡ ምድርም ፡ እጅግ ፡ ፍርያም ፡ ናት ፡፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ፡፡

ወደ ፡ መሥእም ፡ ብዙ ፡ ታናሾች ፡ የንግሊዞች ፡ ደሴቶች ፡ አሉ ፡፡

---

## ፪፪፡፡ ባትላንቲስ ፡ ውቅያኖስ ፡፡

*a.* ቅድስት ፡ ሄሌና ፡ የንግሊዞች ፡ ግዛት ፡፡ ክሊማ ፡ ጤና ፡ ነው ፡ ምድርም ፡ እጅግ ፡ ፍርያም ፡ ናት ፡፡ ባላገሮች ፡ ፳፲፻፡ እንግሊዞችና ፡ ሻንክሎች ፡፡ ከኤውሮጳ ፡ ወደ ፡ ህንድ ፡ ለሚሔዱ ፡ መርከቦች ፡ ማረፊያ ፡ ናት ፡፡ ቦናጳርት ፡ በተመታ ፡ ጊዜ ፡ እንግሊዞች ፡ ይህችን ፡ ደሴት ፡ ግዞትን ፡ አደረጉለት ፡ ከዚያም ፡ ሞተ ፡ ባመት ፡ ፲፰፻፪፡፡

ጀምስተውን ፡ ከተማና ፡ አምባ ፡፡ ሎንግውድ ፡ የቦናጳርት ፡ ቤት ፡ የነበረች ፡ መቃበሩም ፡ ይቀርባል ፡፡

*b.* ያሰንሽን ፡ (የዕርገት ፡) ደሴት ፡፡ የንግሊዞች ግዛት ፡፡

---

የአፍሪቃ ፡ ጌዎግራፊያ ፡ መጨረሻ ፡፡

# አሜሪካ ::

ስ ፡፡ ወ ፡፡ ታት ፡፡ የምብ ፡ ርት ፡ ፶፫°፡ — ፻፷፰°፡፡ ወድ ፡ ከ ፶፯°፡ ከደ ፡ ወድ ፡ ጀምር ፡ እስከ ፡ ሰሜን ፡ መውጫ ፡ ድረ ስ ፡፡ ወደ ፡ ምቅ ፡ ባትለንቲስ ፡ ውቅያኖስ ፡ ወደ ፡ ደ ፡ በመገላ ን ፡ ባሕር ፡ ወደ ፡ ምብ ፡ በጸጥታ ፡ ውቅያኖስ ፡ ወደ ፡ ሰ ፡ በሰ ፡ ውርጭ ፡ ባሕር ፡ ተወሰነች ፡፡ ርዝመትዋም ፡ ፻፻፡ ወርድዋ ም ፡ ፪፲፻ ፡ ሚላ ፡ ስፋትዋም ፡ ፲፭፡ ወይስ ፡ ፲፮፡ ሚልዮን ፡ ሚላ ፡ ታህላለች ፡፡ ከኤውሮጳም ፡ በውርጭ ፡ ባሕርና ፡ ባት ለንቲስ ፡ ውቅያኖስ ፡ ከአፍሪቃም ፡ በአትለንቲስ ፡ ከስያ ም ፡ በጸጥታ ፡ ውቅያኖስና ፡ በቤሪንግ ፡ መንገድ ፡ ተለየች ፡፡

የምድር ፡ ጠባይ ፡፡ ክሊማ ፡ እጅግ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ነው ፡ እንደ ፡ ወርዱ ፡ እንደ ፡ ተራሮችም ፡ እንደ ፡ ባሕሮችም ፡፡ ም ድር ፡ ፍሬያም ፡ ናት ፡ በሰሜን ፡ ጫሪሽ ፡ እንጂ ፡ አንደች ፡ ወደማይበቅል ፡ በብርድ ፡ መክንያት ፡፡ በደቡብም ፡ አንደ ንድ ፡ ጊዜ ፡ ደርቅ ፡ ዘመን ፡ ይመጣል ፡፡ የምድር ፡ መናወጥ ና ፡ ኦርካኖችም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ አሉ ፡፡

ያሜሪካ ፡ ኮንቲነንት ፡ በ፪፡ ታላቆች ፡ ጴኒንሱሎች ፡ ተከ ፈለ ፡ በጳነማ ፡ ወይስ ፡ ደርያ ፡ ኢስትሞስ ፡ ባንድ ፡ የ ሚገጠሙ ፡፡ በሁለታቸውም ፡ መኻከል ፡ በመክሲኮ ፡ ጉ በትና ፡ በክሪኢቦች ፡ ባሕር ፡ የደሴቶች ፡ መሰብሰቢያ ፡ የም ዕራብ ፡ ህንድ ፡ የሚባል ፡ ይገኛል ፡ እርሱም ፡ መኻከለኛ ፡ አሜሪካ ፡ ነው ፡፡

ባሕሮችና ፡ የባሕር ፡ ጉበቶች ፡፡ የሰሜን ፡ ውቅያኖስ ፡ ከአስኪሞ ፡ ባሕር ፡ ጋራ ፡ ከሀድሰን ፡ ከበፊንስም ፡ ከ ጀምስም ፡ ጉበቶች ፡ ጋራ ፡፡ ያትለንቲስ ፡ ውቅያኖስም ፡ ከ ሎረንጽ ፡ ከመክሲኮም ፡ ካመጾኖችም ፡ ጉበት ፡ ጋራ ፡ ከ ብራሲልያና ፡ ከመገላንም ፡ ባሕሮች ፡ ጋራ ፡፡ የጸጥታ ፡ ውቅ ያኖስም ፡ ከጏየኪል ፡ ከኮኮም ፡ ከጳነማም ፡ ጉበቶች ፡ ከ ካሊፎርኒያ ፡ ባሕርም ፡ ጋራ ፡፡ የባሕር ፡ ደጆች ፡፡ የቤሪንግ ፡ የደዊስም ፡ የበፊንስም ፡ የሀድሰንም ፡ የመገላንም ፡ ደጆ

ች ፡፡ ታላቆች ፡ ወንዞች ፡፡ በሰሜን ፡ አሜሪካ ፡፡ ሚሲሲ
ፒ ፡ ሎረንጽም ፡ ኦሀዮም ፡ የሎስቶንም ፡ ሚሱሪም ፡፡ በደ
ቡብ ፡ አሜሪካም ፡፡ የአመጾኖች ፡ ወንዝ ፡ ከምድር ፡ ወን
ዞች ፡ ሁሉ ፡ የሚበልጥ ፡ ጵላታም ፡ ኦሪኖኮም ፡፡ የምድ
ር ፡ ባሕሮችም ፡፡ በሰሜን ፡ አሜሪካ ፡፡ የባሮች ፡ ባሕር ፡፡
የዊኒጰግ ፡ ባሕርም ፡ የላይኛ ፡ ባሕርም ፡ የሁሮን ፡ ባሕርም ፡
የሚቺገን ፡ ባሕርም ፡ የኢርዬ ፡ ባሕርም ፡ የኦንታርዮ ፡ ባሕ
ርም ፡ ብዙ ፡ ሌሎችም ፡፡ በደቡብ ፡ አሜሪካ ፡፡ ጵሪማ ፡ መ
ክሪይቦም ፡ ቲቲካካም ፡፡ ታላቆች ፡ ተራሮች ፡፡ ኮርዲል
ደረስ ፡ ከደቡብ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ የሚሔዱ ፡፡ ከርሳቸውም ፡
አንዱ ፡ ቺምቦረሶ ፡ የሚባል ፡ ከሁሉ ፡ የሚበልጥ ፡ ነው ፡ ከ
ፍታው ፡ ፳፪፻ ፡ አገር ፡ ነውና ፡ ከደወለጊርም ፡ ተራራ ፡ ብቻ ፡
ጥቂት ፡ ያንሳል ፡፡ ሌሎችም ፡ ታላቆች ፡ ተራሮች ፡ እሌህ ፡ ና
ቸው ፡፡ ቶንጉራት ፡ አንቲሳናም ፡ ጰኪንካም ፡፡ ታላቆች ፡ ጵ
ላቶችም ፡ በመክሲኮና ፡ በኵቶ ፡ አሉ ፡፡ ካጾችም ፡፡ የወ
ርቄ ፡ ካጽ ፡ መንደቺኖም ፡ ሉቃስም ፡ ኮረንተስም ፡ ሆርን
ም ፡ ብያንኮም ፡ ሮኹስም ፡ ብርቶንም ፡፡ ምድር ፡ የምታ
ወጣ ፡፡ እጅግ ፡ ወርቅ ፡ ብርም ፡ ጵለቲናም ፡ ነሃስም ፡ ብረ
ትም ፡ አልማስም ፡ ሌሎችም ፡ የከበሩ ፡ ደንጎች ፡፡ ጨው
ም ፡ ኒትረምም ፡፡ ቶምበኮም ፡ ጶታትስም ፡ ከካዎም ፡ ማ
ኽላም ፡ እጅግ ፡ መድኃኒትም ፡ ቡንም ፡ ሡክርም ፡ ጥጥ
ም ፡ የልዩ ፡ ልዩም ፡ የከበረ ፡ እንጨት ፡፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ አራ
ዊትም ፡ ላማም ፡ ፈረስም ፡ ዖፍም ፡ ዓሣም ፡፡

የጅ ፡ ስራ ፡፡ መሻየጥም ፡፡ በሰሜን ፡ አሜሪካ ፡ ሬጱብ
ሊካ ፡ ከሁሉ ፡ ይበልጣል ፡፡

ባላገሮች ፡፡ ፳፤ ወይስ ፡ ፪፤ ሚልዮን ፡፡ ከርሳቸውም ፡ ክ
ፍል ፡ ኢንዲያኖች ፡ የሚልዋቸው ፡ የድሮ ፡ ተቀማጮች ፡
ናቸው ፡፡ ክፍልም ፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ አይነት ፡ ፈረንጆች ፡፡ ክፍ
ልም ፡ የተደባለቁ ፡ ሰዎች ፡፡ ኢንዲያኖችም ፡ በፍጥረታቸ
ው ፡ አረማውያን ፡ ናቸው ፡ ተከፍለው ፡ ግን ፡ በወንጌል ፡
መለክተኞች ፡ ትምህርት ፡ በእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ሃይ
ማኖትን ፡ ተቀበሉ ፡፡ ደግሞም ፡ ብዙ ፡ ኾንክሎች ፡ አሉ ፡ በ
ባሮች ፡ ነጋደች ፡ ካገራቸው ፡ ተይዘው ፡ ወደ ፡ አሜሪካ ፡ ለ

ብርቱ ፡ ባርነት ፡ የተሼጡ ። በንግሊዝ ፡ ግዛት ፡ ግን ፡ የነበሩ ፡ ባሮች ፡ ሁሉ ፡ ባመት ፡ ፲፰፻፴፬፡ ከእንግሊዞች ፡ ፍቅር ፡ የተነሣ ፡ አርነት ፡ ወጡ ። ያልተማሩም ፡ ትምርትን ፡ ገቡ ። መንግሥታችንም ፡ ለጌቶቻቸው ፡ ፳፡ ሚልዮን ፡ ብር ፡ ሰጠች ፡ ባሮቻቸውን ፡ በመፍታት ፡ እንደይጉዱ ። በመኻከላቸውም ፡ የወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ ያስተምራሉ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በመንፈሱ ፡ ኃይል ፡ የብዙ ፡ ሻንክሎችን ፡ ልብ ፡ ለክርስቶስ ፡ ሃይማኖት ፡ አስገዛ ።

መከፈል ። አሜሪካ ፡ በ፫፡ ክፍል ፡ ትከፈላለች ፡ እርሳቸውም ፡ ፩፡ የሰሜን ፡ አሜሪካ ። ፪፡ የደቡብ ፡ አሜሪካ ። ፫፡ መኻከለኛ ፡ አሜሪካ ፡ ወይስ ፡ የምዕራብ ፡ ኢንዲያ ።

---

## ፩፡ የሰሜን ፡ አሜሪካ ።

### 1. የበፌንስ ፡ ጉበት ፡ ምድሮች ።

የበፌንስ ፡ ጉበት ፡ በሰሜን ፡ መውጫ ፡ ዙርያ ፡ አለች ። ሁለት ፡ መግቢዮችም ፡ አልዋት ፡ የዴዊስ ፡ መንገድ ፡ በምቅ ፡ የበፌንስ ፡ መንገድም ፡ በምዕራብ ። በዙርያዋ ፡ ያሉ ፡ ምድሮችም ፡ ወትሩ ፡ ውርጭን ፡ ይለብሳሉ ፡ ብርድም ፡ እጅግ ፡ ነው ።

### ፩፩፡ ግሪንላንድ ።

በእስኪሞ ፡ ባሕርና ፡ በዴዊስ ፡ መንገድ ፡ ተወሰነች ። የወንጌል ፡ ወንድሞች ፡ ጉባኤ ፡ መለክተኞቻቸው ፡ ወንጌልን ፡ ይዘው ፡ ወደዚች ፡ ምድር ፡ ሔዱ ፡ ባላገሮችም ፡ በቀደም ፡ አረማውያን ፡ የነበሩ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡ ክርስቲያን ፡ ሆኑ ። አያሌ ፡ የትኩስ ፡ ውኃ ፡ ምንጮች ፡ አሉ ። ከብርድም ፡ የተነሣ ፡ አታክልት ፡ አይበቅሉም ፡ በደቡብ ፡ እንጅ ፡ አንደንድ ። ከንስሳና ፡ ከሚነራል ፡ መንግሥትም ፡ የሚገኝ ፡ ይህ ፡ ነው ። ሬንዲር ፡ ውሻም ፡ የባሕር ፡ ውሻም ፡ የባሕር ፡ ፈረስም ፡ ዌልም ፡ ጥቍርና ፡ ነጭ ፡ ቢርም ፡ ቀበሮም ፡ ነጭ ፡ ጢንቸልም ፡ ቢሉርም ፡ አስቤስትም ፡ እብነ ፡ በረደም ፡ ደንም ፡ የደንጊያ ፡ ከሰልም ፡ ሌሎች ፡ ሚነራሎችም ።

ለደንማርክ : ንጉሥ : አያሌ : ግዛት : ከዚህ : አለች :: የወንጌል : ወንድሞችም : ኮሎኒዮች : እሌህ : ናቸው :: አዲስ : ሀርንሁት :: ሊኽተናውም : ሊኽተንፈልስም ::

## ፲፱ :: ስጲጽበርግን ::

ከሁሉ : ይልቅ : ወደ : ሰሜን : ያሉ : ደሴቶች : ናቸው :: ከዚያም : ሌሊት : ሲረዝም : ጊዜ : አምስት : ወር : ትኖራለች :: ቀንም : ሲረዝም : አምስት : ወር :: ወደዚህ : የሚሔዱ : ሰዎች : ዌልንና : የባሕርን : ውሻ : ነጭ : ቤርንም : ቀበሮንም : ሬንዲርንም : ዖፎንም : ለመያዝ : ይሔዳሉ ::

2. በሀድሰን : ጉበት : ዙርያ : ያሉ : ምድር ::

የንግሊዞች : ግዛት :: የሀድሰን : ጉበት : ጉባኤ : ከዚህ : ይሻየጣሉ ::

## ፳፩ :: ለብረደር ::

ታላቅ : ጴኒንሱላ : ናት :: ክሊማ : ብርድ : ነው :: ምድር : የምታወጣ :: የማርያም : ብርጭቆ : አስበስትም : የሚቀርም :: ባላገሮች : እስኪሞችና : ኢንዲያኖች : ናቸው :: በመኻከላቸውም : የወንጌል : ወንድሞች : የክርስቶስን : ትምርት : ያስተምራሉ : ብዙ : ሰዎችም : በክርስቶስ : ያምናሉ ::

ናይን : ኦክክም : ሆጵደልም : የወንድሞች : ኮሎኒዮች ::

ኢስትሜን :: ሪችመንድስፎርትም : የንግሊዞች : ገቢዮች ::

## ፳፪ :: አዲስ : ዌልስ ::

ክሊማና : ምድር : እንደ : ለብረደር :: ታላቅ : ወንዝ : ቸርቺል : ነው :: ባላገሮች : ፱፻፱ እስኪሞች : ጥቂት : ፈርንጆችም ::

ቸርቺል :: ዮርክም :: አልበኒም :: ግሎስትርም : የንግሊዞች : አምቦቾችና : ገቢዮች ::

### 3. የውሥጥና ፡ የመውጫ ፡ ምድር ፡፡

የኢንዲያኖች ፡ ግዛት ፡፡ እርሳቸውም ፡ በብዙ ፡ ነገዶች ፡ ተከፍለው ፡ እጅግ ፡ ሰፊ ፡ ምድርን ፡ ይይዛሉ ፡፡ የወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ በመኻከላቸው ፡ ያስተምራሉ ፡ ከርሳቸውም ፡ ብዙ ፡ አረሚነትን ፡ ትተው ፡ ወደ ፡ እውነተኛ ፡ ሃይማኖት ፡ ደረሱ ፡፡

ወንዞችና ፡ የምድር ፡ ባሕሮች ፡፡ የባሮች ፡ ወንዝና ፡ የባሮች ፡ ባሕር ፡፡ የዊኒጶግ ፡ ባሕርም ፡ የክሌር ፡ ባሕርም ፡ የቸርቺል ፡ ወንዝም ፡ የነሣስ ፡ ጉድጓዶች ፡ ወንዝም ፡፡ ለሀድሰን ፡ ጉበትም ፡ ጉባኤ ፡ ከዚህ ፡ ደግሞ ፡ ብዙ ፡ ስፍሮች ፡ አሉ ፡ ለስራና ፡ ለመሻየጥ ፡፡

---

### 4. የባሕር ፡ ደር ፡ ምድር ፡፡

ከውርጭ ፡ ካጽ ፡ ወደ ፡ ፈረንቸስኮ ፡ መርስ ፡ ተዘረጋች ፡፡ ብዙ ፡ ደሴቶችም ፡ ይቀርባሉ ፡፡ ብዙ ፡ ቡልካኖችም ፡ በዚች ፡ ደር ፡ አሉ ፡፡ ታላቆች ፡ ወንዞችም ፡ ኮሎምቢያና ፡ ልዊስ ፡፡ ባላገሮች ፡ ኢንዲያኖች ፡ ናቸው ፡ ሩሶችም ፡፡

መክፈል ፡፡

፩፩፡፡ የሰሜን ፡ ደር ፡ አያሌ ፡ ግዛት ፡ ለሩሶች ፡ አለ ፡፡

፪፪፡፡ መኻከለኛ ፡ ደር ፡ የሩሶች ፡ ግዛት ፡፡

፫፫፡፡ የደቡብ ፡ ደር ፡ እርሱም ፡ አደስ ፡ አልቢዮን ፡ በ፫፡ ክፍል ፡፡ ደች ፡ ምድርም ፡ ተከፍላ ፡ ለሰሜን ፡ አሜሪካ ፡ ሬጱብሊካ ፡ ተከፍላም ፡ ለንግሊዞች ፡ ትገዛለች ፡፡ አያሌም ፡ ታላቆች ፡ መስኖች ፡ አሉ ፡ መርከቦች ፡ የሚሰሩባቸው ፡፡

የጌዎርጊስ ፡ አርኺጴለጎስ ፡፡ የጵሪንጵዌልስም ፡ አርኺጴለጎስ ፡ ፯፡ ቡልካኖች ፡ ያሉበት ፡፡

---

### 5. የንግሊዞች ፡ ሰሜን ፡ አሜሪካ ፡፡

፹፻፻፡ ወይስ ፡ ፯፻፻፡ ሰዎች ፡ አሉባት ፡፡ በ፱፡ ግዛትም ፡ ተከፈለች ፡፡ ሁላቸውም ፡ በኰበክ ፡ ለሚኖር ፡ ለንግሥት ፡ መስለኔ ፡ ይገዛሉ ፡፡

፩፩፡፡ አይስ ፡ ፈውንድለንድ ፡፡ ምድር ፡ መካን ፡ አየርም ፡ ብርቱ ፡ ነው ፡፡ ፷፲፻፡፡፡ እንግሊዞች ፡ አያሌም ፡ ኢንዲያኖች ፡ ከዚህ ፡ አሉ ፡፡

፪፪፡፡ ፫፫፡፡ አይስ ፡ ስኮትለንድና ፡ አይስ ፡ ብረውንሽወይግ ፡፡ ደን ፡ መልትዋል ፡፡ ፷፻፻፡፡፡ ሰዎች ፡ ከርሳቸውም ፡ ብዙ ፡ እንግሊዞችና ፡ ንምሳውያን ፡፡ ሚክመክም ፡ የሚያሳኙ ፡ የተማረ ፡ ኢንዲያኖች ፡፡

፬፬፡፡ ከነደ ፡ ወይስ ፡ ኩበክ ፡፡ ክሊማ ፡ ጤና ፡ ነው ፡ ምድርም ፡ ፍርያም ፡ ናት ፡፡ የምድር ፡ ባሕሮች ፡፡ ላይኛ ፡ ባሕር ፡ የሁሮን ፡ ባሕርም ፡ የሚቺገን ፡ ባሕርም ፡ የኢሪዬ ፡ ባሕርም ፡ የኦንታርዮ ፡ ባሕርም ፡፡ ሁላቸውም ፡ እርሶ ፡ በርሳቸው ፡ በመስኖች ፡ ይገጠማሉ ፡፡ ምድርም ፡ እጅግ ፡ ፍሬን ፡ ታወጣለች ፡፡ ባላገሮች ፡፡ ፷፻፻፡፡፡ ፍርንጆች ፡ እርሳቸውም ፡ እንግሊዞችና ፡ ፍረንሲሶች ፡፡ ብዙ ፡ ኢንዲያኖችም ፡፡ አምልኳቸውም ፡ በላይኛ ፡ ከነደ ፡ ጵሮተስተንት ፡ በታችኛ ፡ ከነደም ፡ የሮሚያ ፡ መንገድ ፡ ነው ፡፡

A. ላይኛ ፡ ከነደ ፡፡

ዮርክ ፡ በኦንታርዮ ፡ ባሕር ፡ ደር ፡፡ የመኳንንት ፡ መኖርያ ፡ ፲፪፲፻፡፡ ሰዎች ፡፡ ኪንግስትን ፡፡ ኒያጋራ ፡ የሚስዮን ፡ ስፍራ ፡፡

B. ታችኛ ፡ ከነደ ፡፡

ኩበክ ፡ የከነደ ፡ ሁሉ ፡ ከተማ ፡ የመስለኒም ፡ የንግሊዝና ፡ የሮምያ ፡ ኤጲስቆጶሶችም ፡ መኖርያ ፡፡ አምባ ፡፡ ሆስጲታልም ፡፡ ታላቅ ፡ መርስም ፡ ፷፲፻፡፡፡ ሰዎችም ፡፡ ሞንት ፡ ርያል ፡ ፲፪፲፻፡፡ ሰዎች ፡፡

---

6. ያልተገዙ ፡ ኢንዲያኖች ፡ ምድር ፡ በሰሜን ፡ አሜሪካ ፡፡

ከርሳቸውም ፡ አያሌ ፡ የወንጌልን ፡ ትምርት ፡ ተቀበሉ ፡፡ የቀሩም ፡ በአረሚነት ፡ ይቀመጣሉ ፡፡

---

## 7. የሰሜን ፡ አሜሪካ ፡ ሬጱብሊካ ።

ስ ። ወ ። ታት ። የምብ ፡ ርት ፡ ፳፭°፡ — ፵፱°። ወድ ፡ ፷፯°፡ — ፻፳°። ወደ ፡ ሰ ፡ ባደስ ፡ ስኮትለንድና ፡ በክነዲ ፡ ወደ ፡ ምቅ ፡ ባደስ ፡ ብረውንሽወይግና ፡ ባትለንቲስ ፡ ውቅያኖስ ፡ ወደ ፡ ደ ፡ በመክሲኮ ፡ ጉበት ፡ ወደ ፡ ምብ ፡ ባልተገዙ ፡ ኢን ደያኖች ፡ ምድር ፡ ተወሰነች ። ታላቅነትዋም ፡ ፫፷፻፻፡ ሚ ላ ፡ ነው ።

የምድር ፡ ጠባይ ። ክሊማ ፡ ልውጥ ፡ ነው ፡ ምድርም ፡ ደጋ ፡ ርጥብም ፡ ፍርያምም ፡ ናት ። አያሌ ፡ ተራሮች ፡ አ ሉ ። ጉበቶች ። የሎረንጽ ፡ የመክሲኮም ፡ ሌሎችም ፡ ጉ በቶች ። የምድር ፡ ባሕሮች ። ላይኛ ፡ ባሕር ፡ የሚቺገን ፡ ባሕርም ፡ የቸምጵሌን ፡ ባሕርም ። ታላቆች ፡ ወንዞች ። ሚሲሲጲ ፡ ኦህዮም ፡ ሚሱሪም ፡ ሎረንጽም ፡ የሎስቶኘም ፡ ኮነክቲክትም ፡ ሱስኩሀናም ፡ ሌሎችም ። ብዙ ፡ መስኖች ም ፡ አሉ ። የያዕቆብ ፡ መስኖ ፡ ግን ፡ ከሚቀሩ ፡ ይበልጣል ።

ምድር ፡ የምታወጣ ። እጅግ ፡ እንጨት ፡ ዝፍትም ፡ ቅጥራንም ፡ ተርጰንቲንም ፡ ጶታሳም ። ሩዝም ፡ ሌላ ፡ እህ ልም ፡ ጥጥም ፡ ቱልባም ፡ ከነቢስም ፡ ሡክርም ፡ ወይንም ፡ ኢንዲጎም ፡ ሀርም ። ላምም ፡ በግም ፡ ፈረስም ፡ ዓሣም ፡ ዎፍም ፡ አራዊትም ። ጨውም ፡ ብረትም ፡ ነሣስም ፡ እርሳ ስም ፡ እብነ ፡ በረደም ፡ የደንጊያ ፡ ከሰልም ፡ የጨን ፡ መሬ ትም ፡ የጤና ፡ ምንጮችም ።

የጅ ፡ ስራ ። መሻየጥም ። እጅግ ፡ ልዩና ፡ ደህና ፡ ነው ። መርከብንና ፡ ብዙ ፡ ሌላውን ፡ ነገር ፡ በመስራት ፡ ከንግሊዞ ች ፡ ጋራ ፡ እርሶ ፡ በርሳቸው ፡ ይቀደደማሉ ።

ባላገሮች ፡ ፲፰፡ ሚልዮን ፡ ያህላሉ ። ከርሳቸውም ፡ ብ ዙ ፡ ፈርንጆች ፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ ወገን ። በቍጥርና ፡ በኃይል ፡ ግ ን ፡ የሚበልጡ ፡ እንግሊዞች ፡ ናቸው ። ይች ፡ ሬጱብሊካ ም ፡ የንግልጣር ፡ ልጅ ፡ ናት ፡ በቀደምም ፡ የንግሊዝ ፡ መ ንግሥት ፡ ክፍል ፡ ነበረች ፡ ባላገሮች ፡ ግን ፡ ከንጉሣቸው ፡ ጋ ራ ፡ በተጣሉ ፡ ጊዜ ፡ ሀመፀ ፡ ለራሳቸውም ፡ መንግሥትን ፡ ሠሩ ። አምልኳቸውም ፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ ሥርዓት ፡ የክርስቲያ ን ፡ አምልኮ ፡ ነው ። ጥቂት ፡ አይሁድም ፡ ጥቂት ፡ አረማ

ውያንም ፡ አሉ ። ያደነተኞችም ፡ ክርስቲያኖች ፡ ብዙ ፡ አሉ ። እርሳቸውም ፡ በነን ፡ ለማድረግ ፡ የእግዚአብሔርን ም ፡ መንግሥት ፡ ለመዝረጋት ፡ በኃይላቸው ፡ ሁሉ ፡ ይጋደላሉ ። እግዚአብሔርም ፡ ቍጥራቸውን ፡ በየአመት ፡ ያበዛል ። ጉባኤም ፡ ለጉባኤ ፡ ትጨመሪለች ፡ በተቀደሰች ፡ በሃይማኖትና ፡ በፍቅር ፡ አንድነት ። የወንጌልም ፡ መለክተኞች ፡ አያሌ ፡ ከዚች ፡ ሬጹብሊካ ፡ ይወጣሉ ፡ ባሕዛብ ፡ መኻከል ፡ ክርስቶስን ፡ ለማስታወቅ ።

የመንግሥት ፡ መግዛት ። እንደ ፡ ሀልዌትያ ፡ ሬጹብሊካ ፡ ናት ። በብዙ ፡ ክፍልም ፡ ተከፍላ ፡ ኢያንደንድ ፡ ክፍል ፡ ለራሱ ፡ ሸንጎ ፡ አለው ፡ መካሮቹንም ፡ ከሁላቸው ፡ በላይ ፡ ወደሚሆን ፡ ወደ ፡ ታላቅ ፡ ሸንጎ ፡ ይልካል ። ያም ፡ ታላቅ ፡ ሸንጎ ፡ ኮንግረስ ፡ ይባላል ፡ የሬጹብሊካውንም ፡ ጉዳይ ፡ ሁሉ ፡ ይመክሪል ። ከሕዝብም ፡ የተመረጸ ፡ በኮንግረስም ፡ የተሾመ ፡ ገዢ ፡ አለ ፡ ለ፬፤ አመት ፡ የሚገዛ ። የመንግሥትም ፡ ኃይል ፡ ለዚያ ፡ ዘመን ፡ በ፲፪ ፡ ነው ።

የሬጹብሊካ ፡ መከፈል ። በ፴፱፤ ክፍል ፡ ትከፈላለች ። ከርሳቸውም ፡ ፴፰፤ ኢያንደንዴ ፡ ለራሱ ፡ ይገዛሉ ። አንዱ ፡ ግን ፡ ኮሎምቢያ ፡ የሚሉት ፡ የሁላቸው ፡ ገንዘብና ፡ ግዛት ፡ ነው ። ከርሳቸውም ፡ በቀር ፡ የፍሎሪዳ ፡ ክፍል ፡ ሉብቻው ፡ ነው ። እርሳቸውም ፡ በ፬፤ ክፍሎች ፡ በሰሜን ፡ ክፍል ፡ በመኻከለኛ ፡ ክፍልም ፡ በዜብ ፡ ክፍልም ፡ በሊባ ፡ ክፍልም ፡ ይከፈላሉ ።

### ፩፩፤ የሰሜን ፡ ክፍሎች ።

A. አደስ ፡ ሀምጵሺር ፡ ፱፫፻፤ ሚላ ፡ ፴፯፻፻፤ ሰዎች ። ክሊማ ፡ ልውጥ ፡ ነው ። ምድር ፡ ደን ፡ መልቶባታል ።

ፖርትስመት ፡ ብርቱ ፡ ከተማ ፡ ፳፲፻፤ ሰዎች ። ደህና ፡ መርስ ። እጅግ ፡ ስራና ፡ መሻየጥ ።

ኮንኮርድ ፡ ፪፲፻፤ ሰዎች ፡ የገዢ ፡ መቀመጫ ። አከደሚያ ።

አክስትር ፡ አከደሚያ ። የመርከቦች ፡ መስሪዮች ።

ሎንደንደሪ ፡ ፫፲፱፡ ሰዎች ፡፡ አምህርስት ፡፡ ቸስተርፊልድ ፡፡

ሀኖበር ፡ የደርመት ፡ ኮሌጅ ፡ ታላቅ ፡ ማስተማርያ ፡፡

B. በርሞንት ፡ ፱፱፪፻፳፡ ሚላ ፡ ፪፲፳፭፲፬፡ ሰዎች ፡፡

በኒንግተን ፡ ያመረች ፡ ከተማ ፡፡ እጅግ ፡ እህልና ፡ ተልባ ፡፡ የተልባግር ፡ መስሪ.ዮች ፡፡ ሩትለንድ ፡፡ ዊንዝርም ፡፡

C. መሰኩሰጽ ፡ ፳፪፱፡፡ ሚላ ፡፡ ፴፭፱፱፡፡ ሰዎች ፡፡ እጅግ፡ ስራና ፡ መሻየጥ ፡፡ ምድርም ፡ እጅግ ፡ ፈርያም ፡ ናት ፡፡

ቦስተን ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ፡ ፵፲፱፡ ሰዎች ፡፡ ፎርት ፡ ዊልየም ፡፡ ታላቅ ፡ መርስ ፡ ከማበርያ ፡ ግምብ ፡ ጋሪ. ፡ ለመርከቦች ፡፡ ፲፳፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡፡ አከደሚያም ፡፡ አያሌም ፡ የትምርት ፡ ጉባአዮች ፡፡ የሃይማኖትና ፡ የበጎ ፡ ስሪ.ም ፡ አያሌ ፡ ጉባአዮች ፡፡ ብዙም ፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ ስሪ. ፡ መስሪ.ዮች ፡፡

ሳሌም ፡ ፲፫፲፱፡ ሰዎች ፡፡ አከደሚያ ፡፡ ፪፡ መርሮች ፡፡ እጅግ ፡ መሻየጥ ፡፡ ኬምብርጅ ፡ ፫፲፱፡ ሰዎች ፡፡ ኡኒዌርሲታስ ፡፡ የከዋክብትም ፡ መጠበቅያ ፡፡ ቻርልስተውን ፡፡ ጵሊመት ፡፡

D. ሜን ፡፡ ፪፷፴፲፱፡፡ ሰዎች ፡፡

ዮርክ ፡ ፫፲፱፡ ሰዎች ፡፡ ጶርትለንድ ፡ ፴፲፱፡ ሰዎች ፡፡

E. ሮደይለንድ ፡ ፷፭፱፱፡፡ ሰዎች ፡ ፲፫፹፡፡ ሚላ ፡፡ ምድር ፡ አጅግ ፡ ፈርያም ፡ ናት ፡፡

ጵሮቢደንጽ ፡ ከተማ ፡ ፱፱፡ ሰዎች ፡፡ ኡኒዌርሲታስ ፡፡ ቢብልዮቴካ ፡፡ ብዙ ፡ መስሪ.ዮችም ፡፡ እጅግ ፡ መሻየጥም ፡፡ ንዩጶርት ፡ ደህና ፡ መርስ ፡፡ ፴፲፱፡ ሰዎች ፡፡ አከደሚያ ፡፡ ቢብልዮቴካ ፡፡ ፬፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡፡ ያይሁድ ፡ መስጊድም ፡፡ ደህና ፡ ገቢያ ፡፡ ብሪስትል ፡፡ ወሪክ ፡፡

F. ኮነክቲከት ፡ ፬፳፴፬፡ ሚላ ፡ ፻፭፱፱፡፡ ሰዎች ፡፡ ደግ ፡ ምድር ፡ ናት ፡ ማሳደግዮችም ፡ ማስተማርዮችም ፡ መስሪ.ዮችም ፡ በርስዋ ፡ ይበዛሉ ፡፡

ሀርትፎርድ ፡ ፬፲፱፡ ሰዎች ፡ የጎንጎ ፡ መኖርያ ፡፡ ንዩሄብን ፡ ፳፲፱፡ ሰዎች ፡፡ ኡኒዌርሲታስ ፡ መርስም ፡፡ የቶምበኮም ፡ የክርታስም ፡ የቆርበትም ፡ ብዙ ፡ መስሪ.ዮች ፡፡ እጅ

ግ ፡ መሻየጥም ፡፡ አዲስ ፡ ሎንደን ፡ ብርቱ ፡ መርስ ፡ ደህ ና ፡ ገቢያም ፡ ፫፲፱፡ ሰዎችም ፡፡ ፌርፊልድ ፡ አክደሚያ ፡፡ ሚድልተውን ፡ ታላቅ ፡ ገቢያ ፡፡

ኢሌህም ፡ ፯፡ ክፍሎች ፡ ደግሞ ፡ ባንድ ፡ ስም ፡ አዲስ ፡ እንግልጣር ፡ ይባላሉ ፡፡

፲፪፡፡ መካከለኞች ፡ ክፍሎች ፡፡

G. ንዩዮርክ ፡ ፶፫፲፱፡ ሚላ ፡ ፪፡ ሚልዮን ፡ ሰዎችም ፡፡ ደህች ፡ ክፍልም ፡ እጅግ ፡ ባለጠጋ ፡ ናት ፡፡

ንዩዮርክ ፡ ታላቅ ፡ ያመረችም ፡ ባለጠጋም ፡ ከተማ ፡፡ ፲፯፻፻፡ ሰዎች ፡፡ የመካንንት ፡ መኖርያ ፡፡ ደግ ፡ መርስም ፡፡ ብዙ ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናትም ፡ ለመለያዩት ፡ ሁሉ ፡፡ የኒፍጥም ፡ የመድፍም ፡ ታላቅ ፡ መሰብሰቢያ ፡፡ ኡኒቬርሲታስም ፡፡ ብዙም ፡ የትምርት ፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ በጎ ፡ ስራም ፡ የሚስዮንም ፡ የመጽሐፍ ፡ ቅዱስም ፡ ጉባኤዎች ፡፡ ፶፡ የመጻሕፍት ፡ መጓተምዮች ፡፡ አያሌ ፡ ቢብልዮቴኮችም ፡፡ ብዙ ፡ ማስተማርዮችና ፡ መስሪዮችም ፡፡ እጅግ ፡ መሻየጥም ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡፡

አልበኒ ፡፡ ሀድስን ፡፡ የሪችመንድና ፡ የሎንግ ፡ አይለንድም ፡ ደሴቶች ፡፡

H. ንዩጀርሴ ፡፡ ፯፯፻፡፡ ሚላ ፡፡ ፪፵፫፭፳፪፡ ሰዎች ፡፡

ትረንተን ፡ ከተማ ፡፡ ፻፻፡ ሰዎች ፡፡ አክደሚያ ፡፡ አዲስ ፡ ብረንስዊክ ፡ ፫፲፻፡ ሰዎች ፡፡ ኡኒቬርሲታስ ፡፡

I. ጰንሲልዋኒያ ፡፡ ፵፬፲፻፡ ሚላ ፡፡ ፩፡ ሚልዮን ፡ ፲፫፻፻፡፡ ሰዎች ፡፡

ፊለደልፊያ ፡ ታላቅና ፡ ያመረች ፡ ከተማ ፡ ፻፡፳፻፲፯፡ ሰዎች ፡፡ ኡኒቬርሲታስ ፡፡ የትምርትና ፡ የሃይማኖት ፡ የበጎ ፡ ስራም ፡ የሚስዮንና ፡ የመጽሐፍ ፡ ቅዱስም ፡ ጉባኤዎች ፡፡ ብዙ ፡ ማስተማርዮችና ፡ መስሪዮችም ፡፡ ደህና ፡ ሆስጲታልም ፡፡ ከ፶፡ የሚበዙም ፡ የመጽሐፍ ፡ መጓተምዮች ፡፡ ብዙም ፡ የሥእል ፡ መጓተምዮች ፡፡ ብዙ ፡ ገቢዮችም ፡፡ መቅረጫም ፡፡ ፴፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናትም ፡፡

ጀርመንተውን ፡ የንምሳውያን ፡ አገር ፡፡ ለንክስት

ር :: ኤፍራታ :: ቤተልሔም ፡ የወንጌል ፡ ወንድሞች ፡ ኮሎኒያ ፡ የኤጲስቆጶሳቸውም ፡ መኖርያ ::

ናዝሬት :: ግናድንታልም :: ቤቴልም :: ወሪክም :: ሄብሮንም :: የወንጌል ፡ ወንድሞች ፡ ኮሎኒዮች :: ሀርሞኒያ ፡ የሴጰራቲስቶች ፡ ኮሎኒያ ::

K. ደለዋር :: ፪፪፻፡ ማላ :: ፻፻፡ ሰዎች ::

ንዩካስትል ፡ ፲፫፲፻፡ ሰዎች :: ዊልሚንግተን :: ደበር ፡ የመኳንንት ፡ መኖርያ ::

L. ኦህዮ ፡ ፵፲፻፡ ሚላ :: ፶፻፻፡ ሰዎች ::

ሲንሲናቲ ፡ ያመረች ፡ ከተማ ፡ ፰፲፻፡ ሰዎች :: ግናድንሁትን :: ሳሌምም :: ኼንብሩንም ፡ ሊኽተናውም :: የወንጌል ፡ ወንድሞች ፡ ኮሎኒዮች ::

## ፫፫፡ የአዜብ ፡ ክፍሎች ::

M. መሪለንድ ፡ ፶፬፻፻፡ ሰዎች ::

አነጾሊስ ፡ ከተማ ፡ ፯፲፻፡ ሰዎች :: በልቲሞር ፡ ፹፲፻፡ ሰዎች :: ፲፬፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናትም :: ብዙ ፡ ማስተማርዮችና ፡ መስሪዮችም :: አጅግ ፡ መኻየጥም :: ታላቅ ፡ መርስም ::

N. ቢርጊኒያ ፡ ፫፲፻፡ ሚላ :: ፩፡ ሚልዮን ፡ ፰፬፻፡ ሰዎች ::

ሪችመንድ ፡ ከተማ ::

O. የሰሜን ፡ ከሮሊና ፡ ፵፰፲፻፡ ሚላ :: ፰፻፻፡ ሰዎች ::

ረሌ ፡ ከተማ :: አደስ ፡ ቤርን ፡ ታላቅ ፡ የሀልዌትያ ፡ ሰዎች ፡ ኮሎኒያ :: ቢታኒያና ፡ ቤተበራ ፡ የወንጌል ፡ ወንድሞች ፡ ኮሎኒዮች ::

P. የደቡብ ፡ ከሮሊና ፡ ፳፬፲፻፡ ሚላ :: ፰፻፻፡ ሰዎች ::

ቻርልስተውን ፡ ታላቅ ፡ ያመረችም ፡ ከተማ ::

Q. ጊዎርጊያ ፡ ፰፲፻፡ ሚላ :: ፵፻፻፡ ሰዎች ::

## ፬፬፡ የሊባ ፡ ክፍሎች ::

R. ተነሢ ፡ ፵፲፻፡ ሚላ ፡ ፺፻፻፡ ሰዎች ::

S. ከንተኪ ፡ ፵፻፲፡ ሚላ ፡ ፫፻፻፡ ሰዎች ::

T. አደስ ፡ ኦርልያንስ ፡ ፲፫፻፻፡ ሰዎች ::

አደስ ፡ ኦርሊያንስ ፡ ከተማ ። ታላቅ ፡ ገቢያ ። ፵፲፻ ሰዎች ። የመጽሐፍ ፡ ቅዱስና ፡ የሚስዮን ፡ ጉባኤዎች ። ብዙ ፡ መስሪዎችም ።

U. ሚሲሲጲ ፡ ፵፯፲፻ ሚላ ፡ ፲፼ ሰዎች ።

V. ኢንዲያና ፡ ፴፫፲፻ ሚላ ፡ ፲፼ ሰዎች ።

W. ኢሊንዋ ፡ ፶፲፻ ሚላ ፡ ፰፼ ሰዎች ። ከርሶቸውም ፡ ብዙ ፡ ኢንዲያኖች ፡ በመኻከላቸውም ፡ የወንጌል ፡ መልክተኞች ፡ ያስተምራሉ ።

X. ሚሶሪ ፡ ፺፰፯፻ ሚላ ፡ ፲፼ ሰዎች ። ከዚያም ፡ የወንጌል ፡ መልክተኞች ፡ በኢንዲያኖች ፡ መኻከል ፡ ይሰራሉ ።

የሬጱብሊካ ፡ ሁሉ ፡ ገንዘብ ፡ ይህ ፡ ነው ።

*a.* የኮሉምቢያ ፡ ግዛት ። *b.* የፍሎሪዳ ፡ ግዛት ። *c.* የሚቺገን ፡ ግዛት ። *d.* አያሌ ፡ ከኢንዲያኖች ፡ የወሰዱዋት ፡ ምድር ።

ወሺንግተን ፡ የሬጱብሊካ ፡ ሁሉ ፡ ከተማ ፡ በኮሉምቢያ ፡ ግዛት ። የኮንግረስ ፡ መሰብሰቢያ ። እጅግ ፡ መሻየጥ ።

---

8. አያሌ ፡ ምድሮች ፡ በሰሜን ፡ አሜሪካ ፡ በቀደም ፡ የስጳኒያ ፡ ግዛት ፡ የነበሩ ።

፩፩። አደስ ፡ መክሲኮ ።

ወደ ፡ ሰ ፡ ባልተገዙ ፡ ኢንዲያኖች ፡ ምድር ፡ በሰሜን ፡ አሜሪካ ፡ ሬጱብሊካም ፡ ወደ ፡ ደ ፡ በመክሲኮ ፡ ወደ ፡ ምቅ ፡ በሰሜን ፡ አሜሪካ ፡ ሬጱብሊካ ፡ ወደ ፡ ምብ ፡ በከሊፎርንያና ፡ በጹርጹር ፡ ባሕር ፡ ተወሰነች ። ባላገሮች ፡ ፍርንጆችና ፡ ኢንዲያኖች ፡ ናቸው ።

፪፪። አደስ ፡ ነበራ ።

፴፼ ሰዎች ። ተራሮች ፡ እጅግ ፡ ብርን ፡ ያወጣሉ ።

፫፫። ተክሰስ ። አደስ ፡ ሬጱብሊካ ።

፬፬። የከሊፎርኒያ ፡ ጴኒንሱላ ። ፵፲፻ ሰዎች ።

፫፫፤ አርጊት : መክሲኮ ::

፯፤ ወይስ : ፰፤ ሚልዮን : ሰዎች :: ደህች : ምድርም : የ ወርቅና : የብር : መዝገብ : ናት : የምድርም : ፍሬ : ሁሉ : መልቶባታል :: በ፫፤ ክፍል : ተከፈለች ::

A. መክሲኮ :: ፯፤ ሚልዮን : ሰዎች ::

መክሲኮ : ታላቅ : ያመረችም : ባለጠጋም : ከተማ :: ታላቅ : ገቢያ :: ፲፫፻፻፤ ሰዎች :: ብዙ : ገደሞችና : አብያተ : ክርስቲያናት :: ኡኒቬርሲታስ :: አያሌ : ማስተማርዮችና : መስሪ.ዮች ::

አክጱልኮ : መርስ : በጸዋታ : ባሕር :: ታላቅ : ገቢያ ::

ጓደላክሰራ : ፫፲፻፤ ሰዎች :: ኡኒቬርሲታስ ::

B. ሚሪደ : ደዩክታን :: ፶፻፻፤ ሰዎች ::

C. ጓቲማላ : ፩፤ ሚልዮን : ከ፶፻፻፤ ሰዎች ::

---

፪። የደቡብ : አሜሪካ ::

መክፈል :: 1. በቀደም : ለስጳንያ : የተገዙ : ዛሬም : ለ ራ.ሳቸው : የሚኖሩ : ምድሮች :: 2. ዛሬም : ለስጳንያ : የተገ ዛች : ምድር :: 3. ብራ.ሲልያ :: 4. የፈረንጆች : ግዛት :: 5. ያልተገዙ : ኢንደ.ያኖች :: 6. ደሴቶች ::

1. በቀደም : የስጳንያ : ግዛት : የነበሩ : ዛሬ : ግ ን : ለራ.ሳቸው : የሚኖሩ : ምድሮች ::

እርሳቸውም : ኮሎምቢያ : ጴሩም : ኪ.ሊም : ጵላታም :: ሁላቸውም : ሬጱብሊኮች : ናቸው ::

፩፩። የኮሎምቢያ : ሬጱብሊካ :: ፬፤ ሚልዮን : ሰዎች ::

A. ኤደ.ስ : ግረ.ነደ ::

*a.* የጰናማ : ኢ.ስትሞስ :: (ደርደ ::) ጰናማ : ከተማ : ፳፲፻፤ ሰዎች ::

*b.* ቮኮ : አጀግ : ወርቅና : ከካዋ ::

*c.* ከርታግና :: ከርታግና : ከተማ : ፳፫፲፻ : ሰዎች ::

*d.* አንቲዮኪ.ያ :: *e.* ቅድስት : ማርታ :: *f.* ርዮ : ደለ ሀካ ::

*g.* አደስ ፡ ግረነደ ። *h.* ጳጳያን ። *i.* ኩቶ ። ባዚች ፡ ግዛ ት ፡ የቺምቦረሶ ፡ ተራራ ፡ አለ ።

B. ቤኔጽዌለ ። (ካረካስ ።) ፩፡ ሚልዮን ፡ ሰዎች ።

፪፪። የጺሬ ፡ ሬጱብሊካ ። ፩፡ ሚልዮን ፡ ፶፻፻፡ ሰዎች ።
የኮርደልደረስ ፡ ተራሮችና ፡ የአመጾኖች ፡ ታላቅ ፡ ወን ዝ ፡ አሉ ።

፫፫። የኪሊ ፡ ሬጱብሊካ ፡ ፩፡ ሚልዮን ፡ ሰዎች ።

፬፬። ለጽላታ ። ፪፡ ሚልዮን ፡ ሰዎች ።

A. ጶረጓይ ።

በቀደም ፡ የየሱኢቶች ፡ መነኮሶች ፡ ግዛት ፡ ነበረች ፡ ደክ ቶር ፡ ፍረንቺያ ፡ የሚሉት ፡ የሕግ ፡ ተማሪ ፡ በተንኰል ፡ ለ ራሱ ፡ እስኪወስደት ፡ ድረስ ።

B. ለጽላታ ። ፩፡ ሚልዮን ፡ ፶፻፻፡ ሰዎች ።

---

2. ዛሬም ፡ ከስጳኒያ ፡ በታች ፡ ያለች ፡ ምድር ።
ጰተጎኒያ ፡ ሰፊ ፡ መድር ። ጥቂት ፡ ሰዎች ።

---

3. የብራሲልያ ፡ መንግሥት ።

በቀደም ፡ የጶርቱጋል ፡ ግዛት ፡ ነበረች ፡ ዛሬ ፡ ግን ፡ ብቻዋ ን ፡ ናት ። ፫፬፻፻፡ ሚላ ። ባላገሮች ፡ ፬፡ ወይስ ፡ ፫፡ ሚልዮ ን ፡ ሰዎች ።

---

4. የፍርንጀች ፡ ግዛት ።

፩፩። የሆላንድ ፡ ግዛት ።

ሱሪናም ፡ ፲፫፻፻፡ ሰዎች ። የወንጌል ፡ ወንድሞች ፡ ከነዚ ህ ፡ የክርስቶስን ፡ እውቀት ፡ ያስተምራሉ ።
ጰረማሪቦ ፡ ከተማ ፡ ፲፪፲፻፡ ሰዎች ።

፪፪፡፡ የፈረንሲዮች : ግዛት ::

ከየና : ፫፻፻፡ ሰዎች ::

፫፫፡፡ የንግሊዞች : ግዛት :

ጉያና : ፴፻፻፡ ሰዎች :: በርቢስ : የሚስዮን : ስፍራ :: የወንጌል : ወንድሞች : ኮሎኒያ ::

---

5. ያልተገዙ : ኢንዲያኖች : ምድር ::

---

6. የደቡብ : አሜሪካ : ደሴቶች ::

፭፭፡፡ የፈልክላንድ : ደሴቶች : በማግላን : መንገድ ::

፪፪፡፡ የሳት : ምድር : በማግላን : መንገድ ::

---

፫፡፡ መኻከለኛ : አሜሪካ : እርስዋም : የምዕራብ : ኢንዲያ : ደሴቶች ::

ስፍራ :: የሰሜን : ወርድ : ፲°፡—፳፫°፡፡ የምዕራብ : ርዝመት : ፵፱°፡—፹፯°፡ ክሊማ : ለጤና : ክፉ : ነው : ምድር : ግን : ፍርያም : ናት :: ሰዎች : ፪፡ ሚልዮን : ያህላሉ : አርሳቸውም : ፍርንጆች : ክርዮሎችም : ሙላቶችም : ኛንክሎችም :: ኛንክሎችም : በቀድም : በባሮች : መርከቦች : ካገራቸው : ተደዘው : ወደዚህ : መጡ : ለብርቱ : ስራም : ተሼጡ : ባመት : ባመት : ፲፻፻፡ የሚያህል :: እንግሊዞች : ግን : ከሚቀሩ : ከፍርንጆች : ነገሥታች : ጋራ : ተሰማምተው : የባሮችን : መሸየጥ : በግልጽ : ይከለክላሉ :: በግዛታቸውም : የነበሩትን : ባሮች : ሁሉን : አርነት : አወጥዋቸው : ጌቶቻቸውም : እንደይጐዱ : ፱፡ ሚልዮን : ብር : ሰጥዋቸው : ከመንግሥት : መዝገብ :: ይህም : ማድረግ : እጅግ : ደህና : መለወጥን : አደረገ :: የተፈቱ : ባሮች : ደህና : ስራ : ለመዱ :: ሃይማኖትንም : ተማሩ :: መጽሐፍ : ቅዱስንም : ተቀበሉ :: ብዙም : በውነት : ከኃጢአት : ወደ : እግዚአብሔር : ተመለሱ :: ለንግሊዞች : መንግሥትም : ለክብር

ና ፡ ለበረከት ፡ ሆኑ ፡፡ በሌላ ፡ ስፍራ ፡ ግን ፡ የፈራንስና ፡ የስ ጳንያ ፡ ግዛት ፡ በነበረች ፡ በሃይቲ ፡ ደሴት ፡ ቫንክሎች ፡ በጌ ቶቻቸው ፡ ላይ ፡ ዐመፁ ፡ ለራሳቸውም ፡ መንግሥትን ፡ ሠ ሩ ፡፡ አያሌ ፡ ፈረንጆች ፡ ግን ፡ እንግሊዞች ፡ ያደደሉ ፡ ባርነት ን ፡ ገና ፡ አልቫሩም ፡ የባሮችንም ፡ ገቢያ ፡ በግልጽ ፡ ተክለ ክልዋና ፡ በስውር ፡ ያድርጉታል ፡፡ እንግሊዞች ፡ ግን ፡ የባሮች ን ፡ መርከቦች ፡ ይጠብቃሉ ፡ ሲያገኙዋቸውም ፡ ይወስድዋቸ ዋል ፡ ባለመርከቦችንም ፡ ያሥራሉ ፡ ባሮችንም ፡ ፈትተው ፡ ወደ ፡ ሲራ ፡ ሌዎና ፡ ይወስድዋቸዋል ፡ በላይ ፡ እንደየነ ፡፡

መክፈል ፡፡

### 1. ታላቆች ፡ አንቲሎች ፡፡

፩፩፡፡ ኩባ ፡ ከሌህ ፡ ደሴቶች ፡ ሁሉ ፡ የምትበልጥ ፡ ደሴ ት ፡፡ የስጳንያ ፡ ግዛት ፡፡ ፶፻፻፡ ሰዎች ፡ ከርሳቸውም ፡ ፳፻፻፡ ባሮች ፡፡ ምድር ፡ እጅግ ፡ ፍርያም ፡ ናት ፡፡

፪፪፡፡ ጀሜካ ፡ የንግሊዞች ፡ ደሴት ፡፡ ፵፻፻፡ ሰዎች ፡፡ ከዚ ህም ፡ አያሌ ፡ ከወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ ያስተምራሉ ፡፡ የ ንግሊዝ ፡ ኤጲስቆጶስም ፡ መኖርያ ፡፡

፫፫፡፡ ሃይቲ ፡፡ እጅግ ፡ ፍርያም ፡፡ ፩፡ ሚልዮን ፡ ሰዎች ፡፡ በ ቀደም ፡ የፈራንስና ፡ የስጳንያ ፡ ግዛት ፡ ነበረች ፡፡ ደረ ፡ ቫን ክሎችና ፡ ሙለቶች ፡ አሁን ፡ ፵፡ አመት ፡ የሚሆን ፡ በጌቶ ቻቸው ፡ ዐመፁ ፡ ለራሳቸውም ፡ ንጉሥን ፡ ከመካከላቸ ው ፡ አነገሡ ፡፡ እርሱም ፡ ከሸንጎ ፡ ጋራ ፡ ይገዛል ፡፡

፬፬፡፡ ጶርቶ ፡ ሪኮ ፡፡ የስጳንያ ፡ ግዛት ፡ ፲፫፻፻፡ ሰዎች ፡፡

### 2. ታናሾች ፡ አንቲሎች ፡፡

እርሳቸውም ፡ እንደ ፡ ታላቆች ፡ አንቲሎች ፡ ፍርያሞች ፡ ናቸው ፡ ክሊማ ፡ ግን ፡ ለጤና ፡ ይቫላል ፡፡

፩፩፡፡ የቢርጊኒያ ፡ ደሴቶች ፡፡

A. ቅዱስ ፡ ቶማስ ፡፡ የደንማርክ ፡ ግዛት ፡ ፳፲፻፡ ሰዎች ፡፡

B. መስቀል ፡፡ ፴፪፲፻፡ ሰዎች ፡፡ የደንማርክ ፡ ግዛት ፡፡

C. ቅዱስ ፡ ዮሐንስ ፡፡ ፫፲፻፡ ሰዎች ፡፡ የደንማርክ ፡ ግዛ ት ፡፡ በሌህ ፡ ደሴቶችም ፡ የወንጌል ፡ ወንድሞች ፡ የተቀደ ሰውን ፡ ስራቸውን ፡ ለባሮች ፡ ደህንነት ፡ በሃይማኖት ፡ ሰሩ ፡

እግዚአብሔርም ፡ ከርሳቸው ፡ ጋራ ፡ ሁኖ ፡ የብዙን ፡ ልብ ፡ ወደ ፡ ክርስቶስ ፡ አደረገ ::

D. ስጰኒሽተውን :: E. ቶርቶላ :: F. አነጋደ ፡ ከ፲፪፡ ታናሾችም ፡ ደሴቶች ፡ ጋራ ፡ የንግሊዞች ፡ ግዛት ፡ ናቸው ::

፪፪፡ ቅዱስ ፡ ኤውስታኪዮስና ፡ ሳባ :: ፪፡ የሆላንድ ፡ ደሴቶች :: ፳፬፲፻፡ ሰዎች ::

፫፫፡ የቅዱስ ፡ ማርቲን ፡ ደሴቶች ::

A. ቅዱስ ፡ ማርቲን ፡ ፭፲፻፡ ሰዎች :: የሆላንድ ፡ ግዛት ::

B. እንጒላና ፡ በርቡደ ፡ ፫፲፻፡ ሰዎች :: የንግሊዞች ፡ ግዛት ::

C. በርተልሚ ፡ የሽዌደን ፡ ግዛት :: ፳፲፻፡ ሰዎች ::

፬፬፡ የንግሊዞች ፡ ሊወርድ ፡ ደሴቶች ::

A. ክርስቶፋ ፡ ፫፻፻፡ ሰዎች :: B. ልዊስና ፡ ሮደንደ ፡ ፲፮፲፻፡ ሰዎች :: C. ሞንትሰራት :: ፲፩፲፻፡ ሰዎች :: D. አንቲጓ :: ፶፲፻፡ ሰዎች :: ከርሳቸውም ፡ ሁለት ፡ ሲሶ ፡ ሻንክሎች :: በሌህ ፡ አራት ፡ ደሴቶችም ፡ የወንጌል ፡ ስራ ፡ በሻንክሎች ፡ መኻከል ፡ በእግዚአብሔር ፡ በረከት ፡ በጅ ፡ ደላል ::

፭፭፡ የፈረንሲሶች ፡ ደሴቶች :: ጒድሉጵ :: ደሲድራድም :: ማርቲኒክም ፡ ፪፶፭፲፻፡ ሰዎች ፡ አሉባቸው ::

፮፮፡ የንግሊዞች ፡ ደቡብ ፡ ደሴቶች ::

A. ደሚኒካ ፡ ፶፲፻፡ ሰዎች :: B. ሉስያ ፡ ፳፭፲፻፡ ሰዎች :: C. በርባደስ ፡ ፳፻፻፡ ሰዎች :: የኤጲስቆጶስ ፡ መቀመጫ :: D. ቢንሰንት ፡ ፶፲፻፡ ሰዎች :: E. ግሬነደ ፡ ከግሬነደሎች ፡ ጋራ :: ፶፪፲፻፡ ሰዎች :: F. ተባጎ ፡ ፳፭፲፻፡ ሰዎች :: G. ትሪኒደድ ፡ ፬፻፻፡ ሰዎች :: በሌህም ፡ ደሴቶች ፡ የወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ በሻንክሎች ፡ መኻከል ፡ በደስታ ፡ ደሰራሉ ፡ ማስተማራቸው ፡ የተባረከ ፡ ነውና ::

፯፯፡ መርገሬታ ፡ የኮሉምቢያ ፡ ሬጱብሊካ ፡ ደሴት :: ፳፲፻፡ ሰዎች ::

፰፰፡ ኩረሰዎ ፡ የሆላንድ ፡ ግዛት :: ፲፭፲፻፡ ሰዎች ::

3. የበሃማ ፡ (ሉካዮ ፡) ደሴቶች ። የንግሊዞች ፡ ግዛት ።
ሁላቸው ፡ ፳፱፡ ታናናሾችና ፡ ታላቆች ፡ ደሴቶች ፡ ናቸው ፡ ፳፲፱፡ ሰዎች ፡ ያሉባቸው ። ፲፱፡ ብቻ ፡ ከሌሀ ፡ ደሴቶች ፡ የሰው ፡ መኖርያ ፡ ናቸው ። የወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ ከዚህ ፡ ደግሞ ፡ ያስተምራሉ ።

---

## የአሜሪካ ፡ ጌዎግራፊያ ፡ መጨረሻ ።

---

## አውስትራልያ ።

### የደቡብ ፡ ዎቅያኖስ ፡ ደሴቶች ።

---

አውስትራልያ ፡ የምድር ፡ አምስተኛ ፡ ክፍል ፡ ናት ፡ አሜሪካም ፡ ከተገለጸ ፡ በኋላ ፡ እሌሀ ፡ ደሴቶች ፡ ተገኙ ።

ጠባያቸው ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ነው ፡ ኢየስፍራቸው ። ምድር ፡ የምታወጣ ። የንጀራ ፡ ዛፍ ፡ ጵለታናም ፡ የሡክር ፡ አገደም ፡ ገውዝም ፡ ያምም ፡ ሳጎም ፡ ጰታትስም ፡ ከነቢስም ፡ ሎልም ፡ ብረትም ፡ የደንጊያ ፡ ከሰልም ፡ ጫውም ። ከንጉሩም ፡ እርያም ፡ ውሻም ፡ ተኵላም ፡ ድመትም ፡ አ.ልቲስም ፡ ልዩ ፡ ልዩም ፡ ብዙ ፡ እንስሳ ፡ ብዙ ፡ ዖፎም ፡ዓሣም ።

ባላገሮች ። ፪፡ ሚልዮን ፡ ናቸው ። በፍጥረታቸውም ፡ አረማውያን ፡ ከርሳቸውም ፡ ብዙ ፡ የሰውን ፡ ሥጋ ፡ ደበሉ ፡ የተማረኩትንም ፡ ደም ፡ ደጠጡ ፡ ነበሩ ። ዛሬ ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ ደሴቶች ፡ ወንጌልን ፡ ተቀብለዋልና ፡ እውነተኛውን ፡ አምላክ ፡ ያመልካሉ ፡ በጠባያቸውም ፡ ተለውጠው ፡ ባልንጀራቸውን ፡ እንደ ፡ ነፍሳቸው ፡ ደወደሉ ። ዛሬም ፡ ከርሳቸው ፡ ብዙ ፡ ደወጣሉ ፡ ወንጌልን ፡ ባረማውያን ፡ መኻከል ፡ ያስተምሩ ፡ ዘንድ ።

## ፩። አዲስ ፡ ሆላንድ ።

ስፍራ ። የምቅ ፡ ርት ፡ ፻፲፫°፡ — ፻፵፫°። የደ ፡ ወድ ፡ ፲°፡ — ፵°። ይህች ፡ ከምድር ፡ ደሴቶች ፡ ሁሉ ፡ የምትበልጥ ፡ ናት ፡ ርዝመትዋ ፡ ፪፯፻። ወርድዋም ፡ ፪፲፻። ሚላ ፡ ነው ። ክሊማ ፡ በደቡብ ፡ መኻከለኛ ፡ በሰሜን ፡ ግን ፡ ትኩስ ፡ ነው ። ምድርም ፡ በብዙ ፡ ስፍራ ፡ ፍርያም ፡ ናት ።

ባላገሮች ። አራዊት ፡ አረማውያን ፡ ናቸው ። የወንጌል ፡ መልክተኞች ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ደረሱበት ፡ ስፍራ ፡ ብዙ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ የተመለሱ ፡ ሰዎች ፡ ደገኙ ። የሚጐድዋቸው ፡ ግን ፡ ከኤውርጳ ፡ ታሥረው ፡ ወደዚህ ፡ የሚመጡ ፡ በደለኞች ፡ ናቸው ፡ ተፈትተው ፡ ካገር ፡ ሰዎት ፡ ጋራ ፡ ሲደባለቁ ፡ ጊዜ ።

1. አይነተኛ ፡ አዲስ ፡ ሆላንድ ። የደሴት ፡ ምሥራቅ ፡ ደርቻዋ ፡ አዲስ ፡ ሰውትዌልስ ፡ ትባላለች ፡ በርስዋም ፡ የንግሊዞች ፡ ኮሎኒያ ፡ አለች ፡ ክፉ ፡ አድራጎች ፡ የሠርዋት ። በንግልጣር ፡ ብዙ ፡ በደለኞች ፡ ሞትን ፡ ለሚገባው ፡ ነገር ፡ ያደረጉት ፡ በሞት ፡ ፈንታ ፡ ወዲህ ፡ ይሰደዱሉ ። ከዚህም ፡ አያሌ ፡ ዘመን ፡ ታሥረው ፡ ከተቀመጡ ፡ በኋላ ፡ በጎ ፡ ቢያድርጉ ፡ ይፈታሉ ፡ ምድርንም ፡ ያርሳሉና ፡ ይጠቀማሉ ።

ሲድኔ ፡ አዲስ ፡ ከተማ ፡ የንግሊዝም ፡ መስለኒ ፡ መናርያ ፡ የኤጲስቆጶስም ፡ መቀመጫ ፡ ፪፻። ሰዎች ። የኦርፋኖች ፡ ቤትም ፡ ሆስጲታልም ፡ የከዋክብትም ፡ መጠበቅያ ።

2. ፈንደ መንስለንድ ። ከአዲስ ፡ ሆላንድ ፡ ወደ ፡ ደቡብ ። ከዚህም ፡ ሁለተኛ ፡ የበደለኞች ፡ ኮሎኒያ ፡ አለች ።

---

## ፪። አዲስ ፡ ሴላንድ ፡

ሁለት ፡ ደሴቶች ፡ ናቸው ፡ ስፋታቸው ፡ ፺፪፲፻። ሚላ ፡ የሚሆን ፡ የንግሊዝም ፡ ግዛት ፡ ናቸው ። ክሊማ ፡ ደህና ፡ ነው ። ባላገሮች ፡ ፹፻፻። ያህላሉ ። እርሳቸውም ፡ ከጥቂት ፡ አመት ፡ በፊት ፡ ሰውን ፡ ባዮች ፡ ነበሩ ፡ እርሱ ፡ በርሳቸውም ፡ ወትሩ ፡ ተጠልተው ፡ ደፈጁ ፡ ነበሩ ። አሁን ፡ ግን ፡ ፷፯። አመት ፡ የሚሆን ፡ አንድ ፡ ከወንጌል ፡ መልክተኞች ፡

ገባቸው ፡ በመኻከላቸውም ፡ በወንጌል ፡ ማስተማረን ፡ ጀ
መረ ፡ በኋላም ፡ ሌሎች ፡ ከወንድሞቹ ፡ ተጨመረለት ፡፡ ዛ
ሬም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ምህረት ፡ የሕዝብ ፡ ታላቅ ፡ ክፍ
ል ፡ በክርስቶስ ፡ ያምናሉ ፡፡ በውነትም ፡ የክርስቲያንን ፡
አካሔድ ፡ ይመላለሳሉ ፡፡ ብዙ ፡ የሚስዮን ፡ ቦታች ፡ በዚ
ች ፡ ደሴት ፡ አሉ ፡፡

## ፫፡፡ አዲስ ፡ ካሌዶኒያ ፡፡

፭፻፱፡ ሰዎች ፡ አሉባት ፡፡ ገና ፡ በአረማውያን ፡ ጨለማ ፡
ኑረው ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡ በጾር ፡ ይፈጀሉ ፡፡

## ፬፡፡ አዲስ ፡ ጊኔያ ፡፡

## ፭፡፡ አዲስ ፡ ብርታንያና ፡ አዲስ ፡ አርላንድ ፡፡

## ፮፡፡ አዲስ ፡ ጌዎርጊያ ፡ ወይስ ፡ የሰሎሞን ፡ ደሴቶች ፡፡

## ፯፡፡ የሸርሎታ ፡ ደሴቶችም ፡

## ፰፡ አዲስ ፡ ህብሪደች ፡ ወይስ ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ደሴቶች ፡፡

እሌህ ፡ ደሴቶች ፡ ሁሉ ፡ ገና ፡ የወንጌልን ፡ ብርሃን ፡ አላ
ዩም ፡ በአረሚነት ፡ ይኖራሉ ፡ እንጅ ፡ እርሱ ፡ በርሳቸውም ፡
ይፈጀሉ ፡፡

## ፱፡፡ የወደጅነት ፡ የፊጅም ፡ የመርከበኞችም ፡ ደሴ ቶች ፡፡

የወደጅነት ፡ ወይስ ፡ የቶንጋ ፡ ደሴቶች ፡ ፪፯፡ ናቸው ፡፡ በ
ርሳቸውና ፡ በፊጅ ፡ ደሴቶችም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ስራ ፡
ለሰው ፡ ዘላለም ፡ ደህንነት ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡፡ የወንጌል ፡ መ
ለክተኞች ፡ ባመት ፡ ፲፰፻፳፮፡ በመጀመርያ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ወደ
ጅነት ፡ ደሴቶች ፡ ሲደርሱ ፡ ባላገሮች ፡ በኃጢአት ፡ ሁሉ ፡

ይረክሱ ፡ ነበሩ ፡ ጣዖታትን ፡ በማምለክ ፡ በዝሙትም ፡ በጸላትነትም ፡ በመግደልም ። ልጆቻቸውን ፡ ይገድሉ ፡ ነበሩ ። በጾርም ፡ የማረኩትን ፡ የጸላቶቻቸውን ፡ ሥጋ ፡ ይበሉ ፡ ደማቸውንም ፡ ይጠጡ ፡ ነበሩ ። የወንጌል ፡ መለክተኞችም ፡ አያሌ ፡ ወራት ፡ በመኻከላቸው ፡ በከንቱ ፡ ከደከሙ ፡ በኋላ ፡ ባላገሮች ፡ አወጥዋቸው ። በኋላ ፡ ግን ፡ ሁለተኛ ፡ ጊዜ ፡ ማስተማሪቸውን ፡ ፈተኑ ። ከጅግ ፡ ድካምም ፡ ከጅግ ፡ መከራም ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስራቸውን ፡ ባረከ ፡ ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ከኃጢአታቸው ፡ ተመለሱ ። ዛሬም ፡ በሌህ ፡ ደሴቶች ፡ ያደነተኞች ፡ ምእምናን ፡ ቍጥር ፡ ታላቅ ፡ ነው ። ንጉሥም ፡ ክርስቲያን ፡ ሁኖ ፡ መምህራኑን ፡ በወንጌል ፡ ስራቸው ፡ እጅግ ፡ ያግዛቸዋል ። በፊጅ ፡ ደሴቶችም ፡ እንደዚህ ፡ ነው ። የርሳቸው ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ጀርዋቸውን ፡ ቶሎ ፡ ለወንጌል ፡ ከፈቱ ። ዛሬም ፡ ንጉሣቸው ፡ ባለቤቱ ፡ የሕዝቡ ፡ መምህር ፡ ሆነ ። በየእሑድም ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በወንጌል ፡ ይሰብካል ።

---

፲፡ የጉባኤ ፡ ደሴቶች ፡ ከጌወርጊስ ፡ ንጉሥ ፡ ደሴቶች ፡ ጋራ ።

የጉባኤ ፡ ደሴቶች ፡ ፲፩ ታላቆች ፡ አያሌ ፡ ታናኖችም ፡ ናቸው ። ባላገሮች ፡ ፲፻፻ ያህላሉ ። እርሳቸውም ፡ በቀደም ፡ እንደ ፡ ወደጅነት ፡ ደሴቶች ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፡ ባረሚነትም ፡ ባርዌነትም ፡ ሁሉ ፡ ይረክሱ ፡ ነበሩ ። ባመት ፡ ፲፰፻፸፫ ግን ፡ የሎንደን ፡ ሚስዮን ፡ ጉባኤ ፡ ፴ ከወንጌል ፡ መለክተኞች ፡ ሰደደላቸው ፡ ኦተሀይቲ ፡ በሚልዋት ፡ ደሴት ፡ የተቀመጡ ። የኦተሀይቲም ፡ ንጉሥ ፡ ደጠብቃቸው ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ አስደረገ ። እርሳቸው ፡ ግን ፡ ትምርታቸውን ፡ በጀመሩ ፡ ጊዜ ፡ ታላቅ ፡ ስደት ፡ ሆነባቸው ። ከርሳቸውም ፡ ፫ ተገደሉ ፡ የቀረም ፡ ተሳደደ ፡ ደሴትንም ፡ ተው ፡ ፫ ብቻ ፡ ቀረባት ። በኋላም ፡ ፲፩ ተጨመረላቸው ። በብዙ ፡ አመትም ፡ አንደንድ ፡ ብቻ ፡ ካገር ፡ ሰዎች ፡ ሃይማኖትን ፡ ተቀበለ ። የንጉሥ ፡ ልቡም ፡ በውነት ፡ አልጸናም ። በኋላም ፡ ሁ

ከት ፡ ሆነ ፡ ንጉሥም ፡ እርሱ ፡ ከነበረባት ፡ ደሴት ፡ ከኦተሀደቲ ፡ አደሚዉ ፡ ወደምትባል ፡ ወደ ፡ ቀረበች ፡ ደሴት ፡ ሸሸ ፡ የወንጌልን ፡ መለክተኞች ፡ የክርስቲያንም ፡ ታናሽ ፡ ጉባኤ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ይዞ ፡፡ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ሁለት ፡ ጸዋ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ኦተሀደቲ ፡ ተመለሰ ፡ የምእምናንም ፡ ቍጥር ፡ በጥቂት ፡ በጥቂት ፡ በዛ ፡፡ ያረማውያን ፡ ጸላትነት ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ነበረች ፡፡ እርሳቸውም ፡ ክርስቲያንን ፡ ሁሉን ፡ ከንጉሥ ፡ ጋራ ፡ ለመግደል ፡ ተባበሩ ፡፡ ክርስቲያንም ፡ በሁድ ፡ እንደደሰሩ ፡ አውቀዋልና ፡ የሁድን ፡ ቀን ፡ አደረጉ ፡ በመቅደስ ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡ ደወድቁባቸው ፡ ዘንድ ፡ ደገድልዋቸውም ፡ ዘንድ ፡፡ ክርስቲያንም ፡ ደህነን ፡ ፈርተው ፡ እቃ ፡ ጦራቸውን ፡ ደዘው ፡ ለጸሎት ፡ በመቅደስ ፡ ተሰበሰቡ ፡፡ በተሰበሰቡም ፡ ጊዜ ፡ መለክተኛ ፡ መጣላቸው ፡ ጸላቶችም ፡ መጡ ፡ አለ ፡፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታምነው ፡ በሥርዓት ፡ ወጡ ፡ ጸላትንም ፡ ተዋጉ ፡፡ አያሌም ፡ ከመዋጋት ፡ የተከለከሉ ፡ ነበሩ ፡ እርሳቸውም ፡ በጉልበታቸው ፡ ተንበርክከው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸሩ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሰማቸው ፡፡ ዝምታ ፡ ብርቱ ፡ ሆነ ፡ የክርስቲያን ፡ ቍጥር ፡ ጥቂት ፡ ኑርዋልና ፡ ያረማውያንም ፡ ቍጥር ፡ በዛ ፡፡ አያሌ ፡ ሰዓትም ፡ ከተዋጉ ፡ በኋላ ፡ ክርስቲያን ፡ ድል ፡ ነሡ ፡ ጸላቶቻቸውንም ፡ መቱ ፡ ብዙንም ፡ ማረኩ ፡፡ የወትረም ፡ ልማድ ፡ ደህ ፡ ነበረ ፡ የተማረኩትን ፡ ሰዎች ፡ መግደል ፡ ሥጋቸውንም ፡ መብላት ፡ ደማቸውንም ፡ መጠጥ ፡፡ እሌህ ፡ ክርስቲያን ፡ ግን ፡ እርሳቸው ፡ የማረኳቸውን ፡ ጸላቶቻቸውን ፡ አርነት ፡ አወጥዋቸው ፡ ቸርነትንም ፡ አድርገው ፡ ወደ ፡ ቤቶቻቸው ፡ ሰደድዋቸው ፡፡ በዚህም ፡ ፍቅር ፡ ያረማውያን ፡ ልብ ፡ ተመታ ፡ ሁላቸውም ፡ ባንድ ፡ ምክር ፡ ጣዖታቸውን ፡ በእሳት ፡ ጥለው ፡ የክርስቲያንን ፡ ሃይማኖት ፡ ገቡ ፡ የሰውን ፡ ልብ ፡ በጎ ፡ ታደርገዋለችና ፡ ብለው ፡፡ በኋላም ፡ ጀመረ ፡ ንጉሥ ፡ ታላቅ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ አሠራ ፡ ከወንጌል ፡ መለክተኞችም ፡ ጋራ ፡ ተማክሮ ፡ ከታላላቆቹም ፡ ጋራ ፡ ለመንግሥቱ ፡ አዲስ ፡ ሕግን ፡ ሰራ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ የተመሠረተች

ውን : የቀደመችን : ያረማውያን : ሥርዓት : ሸሮ :: እንደ
ሁም : የክርስቲያን : እቃ : ጾር : አይደለም : የክርስቲያ
ን : ፍቅር : እንጅ : በጣዖታት : ላይ : ድል : ነሣ :: የወንጌ
ል : ትምህርትም : ከኦተሀይቲ : ወጥታ : ወደ : ብዙ : ሌሎ
ች : ደሴቶች : ደረሰች ::
የጌወርጊስ : ንጉሥም : የፊሲካም : የጴንጤም : ደሴቶ
ች : ወደ : ምሥራቅ : ይኖራሉ ::

---

## ፲፩:: የመርኩሰስና : ያንድነት : ደሴቶች ::

ምናልባት : ፲፻፻ ሰዎች : አሉባቸው : እርሳቸውም : ገ
ና : አረማውያን : ናቸው ::

---

## ፲፪:: የመልግሬብ : ደሴቶች ::

እርሳቸውም : ፯ ታናሾች : ደሴቶች : ናቸው :: ወደ : ም
ዕራብም : ያጽማጆች : ደሴቶች : አሉ ::

---

## ፲፫:: የከሮሊና : የጴሌውም : ደሴቶች ::

---

## ፲፬:: የማርያኖችና : የሌቦች : ደሴቶች ::

፭ ናቸው : የስጳንያ : ግዛት ::

---

## ፲፭:: የሰንድዊች : ደሴቶች ::

፲፩ ደሴቶች : ናቸው : ፶፻፻ ሰዎችም : አሉባቸው :: እ
ርሳቸውም : ካያሌ : አመት : በፊት : አረማውያን : ነበሩ :
ዛሬ : ግን : በወንጌል : ስብከት : ወደ : እግዚአብሔር : ተ
መለሱ : የክርስቲያን : መንግሥትም : ሆኑ ::

---

## ፲፮:: የደቡብ : ጌወርጊያና : የሰንድዊች : ምድርም :

እሌህ : ፪ ደሴቶች : ከታወቁት : ወደ : ደቡብም : ከም
ትኖር : ምድር : ጭራሽ : ናቸው ::

---

ተጨረሰች : የጌዎግራፊያ : መጽሐፍ ::

# ተግድፎት ::

በዚች : መጽሐፍ : በጽሬት : ወይስ : በመሳተም : ተሳስ ቶ : የገባ : መቅናትንም : የሚኘ : ተግድፎት :: የቀናም : እንዲህ : ተመለከተ : "          " ::

| ገጽ: | መስምር: | | |
|---|---|---|---|
| ፪፡ | ፮፡ | ከላይ :: | በጽላኔቶችና : በፀሐይን : መኻከል : —:—ጨመር :: |
| „ | ፲፡ ፲፩፡ | „ | እንቍላልን : ይመስላል :: በዚህ : ፈን ታ : "ሞላላ : ነው :" በል :: |
| ፪፡፫፡፮፡፡ | „ | „ | የጽለኔቶች : ወገን :: መጀመርያ : አራ ተኛም : ዘጠኘኛም : አሥረኛም : አ ሥር : አንድኛም : ጽለኔታ : የተባት : ወገን : ይሁኑ :: የቀረም : ያንስት : ወገን :: ስለዚህም : ሁለተኛ : ጽለ ኔታ : ዌኑስ : ነው : አይባል : "ዌኑስ : ናት :" እንጅ :: የሚቀርም : እንደ ዚህ : ይቅና :: |
| ፪፡ | ፩፡ | ከታች :: | ከ፫፰፭፡ በኋላ :—:—ይጨመር :: |
| „ | ፩፡ ፮፡ ፲፫፡ | „ | ስዓት : ወደ : ተገኘ : ሁሉ : በርሱ : ፈ ንታ : "ሰዓት :" ይሁን :: |
| ፯፡ | ፫፡ | ከላይ :: | በፈታችው : ፈንታ : "ፈታቸው :" ይሁን :: |
| „ | ፯፡ ፰፡ | „ | በደከሎች : ፈንታ : "ደቀሎች :" ይሁን :: |
| „ | ፲፡ | ከታች :: | በወኃዊ : ፈንታ : "ውኃዊ :" ይሁን :: |
| ፱፡ | ፲፭፡ | ከላይ :: | በመስብሰቢያ : ፈንታ : "መሰብሰብ ያ :" ይሁን :: |
| „ | ፲፮፡ | ከታች :: | በአፍሪካም : ፈንታ : "አፍሪቃም :" ይሁን :: እንዲሁም : በዚህ : መጽ ሐፍ : ሁሉ :: |
| ፱፡ | ፭፡ | „ :: | በሰንስለት : ፈንታ : "ሰንሰለት :" ይ ሁን :: |

| ገጽ ፡ | መስምር ፡ | | |
|---|---|---|---|
| ፲፤ | ፲፩፤ | ከላይ ፡፡ | በባሽዋ ፡ ፈንታ ፡ "ባሸዋ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፲፪፤ | ፪፤ | " | በየሚፈሱ ፡ ፈንታ ፡ "ከሚፈሱ ፡" ይሁን ፡፡ |
| " | ፲፬፤ | " | በመስተወትን ፡ ፈንታ ፡ "ማስተወትን ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፲፫፤ | ፳፤ | " | በባትምስፈሬም ፡ ፈንታ ፡ "ባትሞስፈሬም ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፲፭፤ | ፲፬፤ | " | "በባሕሮችም ፡ በፈሳሾችም ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፲፯፤ | ፭፤ | " | በለማብዘት ፡ ፈንታ ፡ "ለማብዛት ፡" ይሁን ፡፡ |
| " | ፲፩፤ | ከታች ፡፡ | በየምትደርገውም ፡ ፈንታ ፡ "የምታጸናትም ፡" ይሁን ፡፡ |
| " | ፱፤ | " | በባውቀቱ ፡ ፈንታ ፡ "በውቀቱ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፲፱፤ | ፳፤ | ከላይ ፡፡ | በእንግሊስ ፡ "እንግሊዝ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፳፤ | ፫፤ | " | በያልተቀረጸ ፡ ፈንታ ፡ "የተቀረጸ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፳፩፤ | ፫፤ | " | በበማምለከቸውም ፡ ፈንታ ፡ "በማምለካቸውም ፡" ይሁን ፡፡ |
| " | ፯፤ | ከታች ፡፡ | በጋዞ ፡ ፈንታ ፡ "ገዢ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፳፪፤ | ፪፤ | " | በክርችቲያናትም ፡ ፈንታ ፡ "ክርስቲያናትም ፡፡" ይሁን ፡፡ |
| " | ፩፤ | " | በጸጸሳት ፡ ፈንታ ፡ "ጸጻሳት ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፳፫፤ | ፲፭፤ | ከላይ ፡፡ | በአህጋር ፡ ፈንታ ፡ "አህጉር ፡" ይሁን ፡፡ እንደሁም ፡ ገጽ ፡ ፳፬፤ መስምር ፡ ፳፡፡ |
| " | ፯፤ | ከታች ፡፡ | በይጣላሉ ፡ ፈንታ ፡ "ይጥላሉ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፳፯፤ | ፱፤ | ከላይ ፡፡ | በብሬም ፡ ፈንታ ፡ "በሬም ፡" ይሁን ፡፡ |
| " | ፲፭፤ | " | በተምበኾም ፡ ፈንታ ፡ "ቶምበኾም ፡" ይሁን ፡፡ |
| " | ፱፤ | ከታች ፡፡ | በባካሒደ ፡ ፈንታ ፡ "ባካሔደ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፴፩፤ | ፬፤ | ከላይ ፡፡ | በስዎች ፡ ፈንታ ፡ "ሰዎች ፡" ይሁን ፡፡ |
| " | ፭፤ | " | በብርቱና ፡ በአምባ ፡ በመኻከል ፡ አንደ.ት ፡ —፡— ትጥፈ ፡፡ |

## የመጽሐፉ ፡ ተግድፎት ፡፡

| ገጽ፡ | መስምር፡ | |
|---|---|---|
| ፶፫፡ | ፱፡ | ከታች ፡፡ በማኅተምዮች ፡ ፈንታ ፡ "መኅተምዮች ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፶፬፡ | ፭፡ | ከላይ ፡፡ በኤጲስቆጶስ ፡ ፈንታ ፡ "ኤጲስቆጶስ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፶፭፡ | ፯፡ | ከታች ፡፡ "ኡኒቬርሲታስም ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፷፫፡ | ፩፡ | ከላይ ፡፡ በታችኛ ፡ ምድር ፡ ፈንታ ፡ "ታላቅ ፡ ብርታንያና ፡ ኢርላንድ ፡" ይሁን ፡፡ |
| " | ፮፡ | " በመዝገብን ፡ ፈንታ ፡ "መዝገብ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፷፬፡ | ፯፡ | " በጽብንም ፡ ፈንታ ፡ "ጸብንም ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፷፭፡ | ፮፡ | ከታች ፡፡ "ያስተምርዋቸዋል" ፡ ይሁን ፡ |
| ፷፯፡ | ፰፡ ፲፯፡ | " በቀሰል ፡ ፈንታ ፡ ወትሩ ፡ "ከሰል ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፷፱፡ | ፩፡ | ከላይ ፡፡ በስኮትለግድ ፡ ፈንታ ፡ "ስኮትለንድ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፸፩፡ | ፮፡ | " በንጉሥ ፡ ፈንታ ፡ "ንግሥት ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፸፯፡ | ፱፡ | ከታች ፡፡ በመስሬዮትም ፡ ፈንታ ፡ "መስሬዮች ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፸፰፡ | ፲፡ | ከላይ ፡፡ በመጸጻም ፡ ፈንታ ፡ "መጻጻም ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፸፱፡ | ፫፡ | " በቦኤውሮጳ ፡ ፈንታ ፡ "በኤውሮጳ ፡" ይሁን ፡፡ |
| " | ፲፯፡ | " በየመርከኮችም ፡ ፈንታ ፡ "የመ ርከቦችም ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፹፡ | ፯፡ | " በጫትሮጶሊታን ፡ ፈንታ ፡ "ሜትሮጶሊታን ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፹፩፡ | ፲፫፡ ፲፬፡ | ከላይ ፡፡ በበአሜሪካ ፡ ልባ ፡ ፈንታ ፡ "በሰሜን ፡ አሜሪካ ፡" ይሁን ፡፡ |
| " | ፭፡ | ከታች ፡፡ በበመግንሥት ፡ ፈንታ ፡ "በመንግሥት ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፹፬፡ | ፲፫፡ | " በታላቅነቱም ፡ ፈንታ ፡ "ታላቅነትዋም ፡" ይሁን ፡፡ |

# የመጽሐፍ ፡ ትግድፊት ፡፡

| ገጽ ፡ | መስምር ፡ | |
|---|---|---|
| ፳፱ ፡ | ፳ ፡ | ከታች ፡፡ በየሚያደርግ ፡ ፈንታ ፡ "የሚያደርግ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፷፪ ፡ | ፲፪ ፡ | ከላይ ፡፡ በርዝመቹ ፡ ፈንታ ፡ "ርዝመት ፡" ይሁን ፡" |
| ፷፫ ፡ | ፳ ፡ | „ በመንደር ፡ ፈንታ ፡ "መንደር ፡" ይሁን ፡" |
| ፷፬ ፡ | ፫ ፡ | ከታች ፡፡ በልባ ፡ ፈንታ ፡ "ሰሜን ፡ ምዕራብ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፷፳ ፡ | ፱ ፡ | „ በመጀመርያ ፡ ፈንታ ፡ "መጀመርያ ፡" ይሁን ፡፡ |
| „ | ፲፯ ፡ | „ በግዛች ፡ ፈንታ ፡ "ግዛት ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፹፱ ፡ | ፱ ፡ | ከላይ ፡፡ በተሶማሙ ፡ ፈንታ ፡ "ተሰማሙ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፺፪ ፡ | ፲፩ ፡ | „ በስዎች ፡ ፈንታ ፡ "ሰዎች ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፺፬ ፡ | ፪ ፡ | ከታች ፡፡ በያይችነኞች ፡ ፈንታ ፡ "ያይነተኞች ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፺፭ ፡ | ፫ ፡ | ከላይ ፡፡ በየእግንአብሔርን ፡ ፈንታ ፡ "የእግዚአብሔርን ፡" ይሁን ፡፡ |
| „ | ፲፭ ፡ | „ በይህትም ፡ ፈንታ ፡ "ይህችም ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፻፩ ፡ | ፲ ፡ | „ በማሰተማርዮች ፡ ፈንታ ፡ "ማስተማርዎች ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፻፲፬ ፡ | ፲፪ ፡ ፲፫ ፡ | ከታች ፡፡ በፈረንክፈርት ፡ ፈንታ ፡ "ፍረንክፏርት ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፻፲፯ ፡ | ፬ ፡ | „ በስተራልሱንድ ፡ ፈንታ ፡ "ስትራልሱንድ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፻፸፩ ፡ | ፳ ፡ | ከላይ ፡፡ በመንግድ ፡ ፈንታ ፡ "መንገድ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፻፸፪ ፡ | ፲፩ ፡ | ከታች ፡፡ በሰ ፡ ፈንታ ፡ "ስ ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፻፸፫ ፡ | ፯ ፡ | ከላይ ፡፡ በእርሰቸውም ፡ ፈንታ ፡ "እርሳቸውም ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፻፸፯ ፡ | ፫ ፡ | „ በየሥልንና ፡ ፈንታ ፡ "የሥእልና ፡" ይሁን ፡፡ |
| ፻፹፬ ፡ | ፬ ፡ | „ በልባም ፡ ፈንታ ፡ "መሥእም ፡" ይሁን ፡ |
| ፻፹፭ ፡ | ፲፬ ፡ | „ በበልባም ፡ ፈንታ ፡ "በመሥእም ፡" ይሁን ፡፡ |

## የመጽሐፍ ፡ ተግድፎት ፡፡

| ገጽ፡ | መስምር፡ | | |
|---|---|---|---|
| ፻፹፯፡ | ፲፩፡ | ከታች ፡፡ | በበሉበሰቸውም ፡ ፈንታ ፡ “በሉበሳቸ ውም ፡” ይሁን ፡፡ |
| ፻፹፱፡ | ፲፩፡ | ከላይ ፡፡ | በኤውሮጳና ፡ ፈንታ ፡ “ኤውሮጳና ፡” ይሁን ፡፡ |
| ፻፺፱፡ | ፯፡ | ከታች ፡፡ | በግዛተ ፡ ፈንታ ፡ “ግዛት ፡” ይሁን ፡፡ |
| ፻፳፱፡ | ፲፩፡ | ,, | በልዮ ፡ ልዮ ፡ ፈንታ ፡ “ልዩ ፡ ልዩ ፡” ይሁን ፡፡ |
| ፻፴፫፡ | ፲፡ | ,, | በለይ ፡ ፈንታ ፡ “ላይ ፡” ይሁን ፡፡ |
| ፻፵፫፡ | ፪፡ | ከላይ ፡፡ | በተከፈለ፡ፈንታ፡“ተከፈለች፡፡”ይሁን፡፡ |
| ፻፶፩፡ | ፲፡ | ,, | በያረዊትም ፡ ፈንታ ፡ “ያራዊትም ፡” ይሁን ፡፡ |
| ፻፶፫፡ | ፯፡ | ,, | በክረምንት ፡ ፈንታ ፡ “ክረምት ፡” ይሁን ፡፡ |
| ,, | ፯፡ | ,, | በሒይ ፡ ፈንታ ፡ “ሒደ ፡” ይሁን ፡፡ |
| ፻፶፯፡ | ፲፱፡ | ከታች ፡፡ | በብትስጥ፡ፈንታ፡“ብትሰጥ ፡”ይሁን ፡፡ |
| ,, | ፩፡ | ,, | በቅርጸ ፡ ፈንታ ፡ “ቅርጽ ፡” ይሁን ፡፡ |
| ፻፶፯፡ | ፲፪፡ | ከላይ ፡፡ | በስዎች ፡ ፈንታ ፡ ሰዎች ፡” ይሁን ፡፡ |
| ፻፶፰፡ | ፯፡ | ከታች ፡፡ | በእጅና ፡ በአለፈ ፡ መኻከል ፡—፡—ይ ጨመር ፡፡ |
| ፪፻፯፡ | ፱፡ | ከላይ ፡፡ | በአይነተኞች ፡ ፈንታ ፡ “አይነተኞች ፡” ይሁን ፡፡ |
| ,, | ,, | ,, | ለከወሎ ፡ “ና ፡” ይጨመር ፡፡ |
| ፪፻፲፡ | ፫፡ | ከታች ፡፡ | በእሥላምች ፡ ተከፍላውም ፡ ፈንታ ፡ “እሥላሞች ፡ ተከፍለውም ፡” ይ ሁን ፡፡ |
| ፪፲፫፡ | ፲፫፡ | ከላይ ፡፡ | በምለክተኞችም ፡ ፈንታ ፡ “መለክተ ኞችም ፡” ይሁን ፡፡ |
| ፪፲፰፡ | ፲፪፡ | ,, | በአብያት ፡ ፈንታ ፡ “አብያተ ፡” ይሁን ፡፡ |
| ፪፹፰፡ | ፱፡ | ከታች ፡፡ | በነገሥታች ፡ ፈንታ ፡ “ነገሥታት ፡” ይ ሁን ፡፡ |